አብነት ፡ ሳይሰጥ ፡ መቅሠፍቱ፡ በክ ፡ ሊያደጋርቸው ፡ እንዳይ መጣ ፡ ይመገቡ ፡ ዘንድ ፡ የተ ዘጋጁ ፡ ናቸው ፤ ወይትቀተሉ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ የማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ሴቶች ፡ ልጆች፡ ከእናቶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ከአባቶቻ ቸው ፡ ጋራ ፡ ይሞታሉ ፤ሶበ ፡ ተዐርፍ ፡ መቅሠፍቱ ፡ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ታድ ርባቸዋለች ፤ ታሳልፋቸዋለች ፤ ከመ ፡ ኢትምጻእ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ መቅሠፍቱ ፡ በክ ፡ ልታ ደርጋቸው ፡ እንዳትመጣ ፤ ድኅረ ፡ ትክውን ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ በቸርነቱ ፡ ታግሦ ፡ ታግሦ ፡ ኋላ ፡ ታሳልፋቸዋለች።

## ምዕራፍ ፷፩

### ጉባኤ

፩ ፤ ወርኢኩ ፡ በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ተውህቡ ፡ ለእልኩ ፡ መላእክት ፡ አሕባል ፡ ነዊኃን ፤

በእነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ለእነዚያ መላእክት ፡ ረጃጅሞች ፡ ገመዶች ሲሰጡ ፡ አየሁ ፤ (ሥልጣን) ፤ አን ድም ፡ ደገኛ ፡ አእምሮ ፡ ሲሰጥ ፡ አየሁ ፤

፪ ፤ ወነሥኡ ፡ ሎሙ ፡ ክንፈ ፤ ወሠረሩ ፡ ወሖሩ ፡ መንገለ ፡ መስዕ ፤

ዕውቀትን ፡ (ሥልጣንን)፡ ተቀብ ለው ፡ ወደ ፡ መስዕ ፡ ሄዱ ፤

፫ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአክ ፡ እንዘ ፡ እብል ፡ ለምንት ፡ ነሥኡ ፡ እሉንተ ፡ አሕባለ ፡ ነዊኃነ ፡ ወሖሩ ፤

እሊህን ፡ አእምሮታት ፡ (ረጃጅም ገመዶች፡) ለምን ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ? ብዬ ፡ መልአኩን ፡ ጠየቅ ሁት ፤

፬ ፤ ወይቤለኒ ፡ መልአክ ፡ ዘም ስሌየ ፡ ሖሩ ፡ ከመ ፡ ይመጥኑ ፡ አም ጣናተ ፡ ጻድቃን ፤

ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያለ ፡ መልአክም ፡ የጻድቃንን ፡ ቦታ ፡ ሊሠፍሩ ፡ ገመድ ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ፡ አለኝ ፤ አንድም ፡ የጻድቃንን ፡ ቦታ ፡ ሊያውቁ ፡ ዕውቀትን ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ፤

፭ ፤ ወይቤለኒ ፡ መልአክ ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ እሉ ፡ እሙንቱ ፡ አምጣናተ ፡ ጻድቃን ፤

ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ ባልደረ ባዬ ፡ መልአክም ፡ እሊህ ፡ የጻድ ቃን ፡ መለኪያዎች ፡ ናቸው ፡ አለኝ ፤

ወማዕሠረ ፡ ጻድቃን ፡ ያመጽኡ፡ ከመ ፡ ይትመርጐዙ ፡ ዲበ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

መልአኩም ፡ እሊህ ፡ ሥልጣናት ፡ ለዘለዓለሙ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ያመኑ ፡ ጻድቃን ፡ በእርሱ ፡ ፀንተው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ የጻድ ቃን ፡ አንድነትን ፡ ያመጣሉ ።

፯ ፡ ወይዌጥኑ ፤
በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ መኖር ፡ ይጀምራሉ ።
ወየኀድሩ ፡ ኅሩያን ፡ ምስለ ፡ ኅሩያን፣
ደናግልም ፡ ከደናግል ፡ ጋራ ፡ ይኖራሉ ።

፰ ፡ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ አምጣናት ፡ እለ ፡ ይትወሀቡ ፡ በሃይማኖት ፡ ወያጸ ንዑ ፡ ቃለ ፡ ጽድቅ ።
እሊህ ፡ በታዎች ፡ በሃይማኖት ለጸኑ ፣ በእውነተኛው ፡ ቃል ፡ ጸንተው ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለሠሩ ፡ ሰዎች ፡ የሚሰጡ ፡ ናቸው ።

፱ ፡ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ አምጣናት ፡ ይከሥቱ ፡ ኵሉ ፡ ኅቡዓተ ፡ ለዕመቀ ፡ ምድር ።
እሊህም ፡ ሥልጣናት ፡ በመቃ ብር ፡ የተቀበረውን ፡ ሁሉ ፡ ያስ ነሣሉ ።
ወእለ ፡ ተንኍሉ ፡ እምበድው ።
በምድረበዳ ፡ የተቀበሩትን ።
ወእለ፡ ተበልዑ ፡ እምዓሣተ ፡ ባሕር ።
በባሕር ፡ ሲሄዱ ፡ መርከብ ፡ ተሰብሮባቸው ። ባሕር ፡ አስጥ ሟቸው፡ ዓሣዎች ፡ የበሏቸውን።
ወእምአራዊት ።
አራዊት ፡ የበሏቸውን።
ከመ ፡ ይግብኡ ፡ ወይትመርጐዙ ፡ በዕለተ ፡ ኅሩይ ።
ክርስቶስ ፡ በሚመጣበት ፡ ቀን ፡ ተዋሕደው ፡ ይነሡ ፡ ዘንድ ።
ይጸኑ ፡ ዘንድ ፡ እሊህ ፡ ሥልጣ ናት ፡ ያሥነሳሉ ።

፲ ፡ እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘይትኀጐል ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናስት ።
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ፈርሶ ፡ በስብሶ ፡ የሚቀር ፡ ሰው ፡ የለምና ።
ወአልቦ ፡ ዘይክል ፡ ተኀጕሎተ።
ፈርሶ ፡ በስብሶ ፡ መቅረት ፡ የሚ ቻለው ፡ የለም ።

፲፩ ፡ ወነሥኡ ፡ ትእዛዘ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ በመልዕልተ ፡ ሰማያት ።
በሰማይ ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፡ ትእዛዝን ፡ ተቀበሉ ፤ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ብለው ፡ አመሰ ገኑ ።
ወኃይል ።
ኃይል ፡ ብርቱ ፡ ደካማ ።
ወቃል ።
ጕርናና ፡ ሻካራ ፡ የለም ።
አሐዱ ፣
ሁሉም ፡ አንድ ፡ ነው ።
ወብርሃን ፡ አሐዱ ፡ ከመ ፡ እሳት ፣
ብርሃን ፡ ጸጋቸው ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ አንድ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፤ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተቀብለው ፡ ያበራሉ ።

፲፩ ፡ ወሰውእቱ ፡ መቅድመ ፡ ቃል ፡ ይባርክዎ ፤ ወያሌዕልዎ ።

ቃል ፡ ቀዳማዊ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ እንተስ ፡ በአማን ፡ ጥበብ ፡ ቀዳሚሃ ፡ ንጽሕት ፡ ይእቲ ፡ ቀዳሚ ፡ በኵር ፡ ቃለ ፡ አብ [፩] ፡ እንዲል ፣ አካላዊ ፡ ቃልን ፡ ያመሰግኑታል ፤ አንድም ፡ እንዳለው ፡ ከዝርዋን ፡ ቃላት ፡ አስቀድሞ ፡ የነበረ ፡ አካላዊ ፡ ቃልን ፡ ያመሰግኑታል ፤ አትሪከን ፣ አተርጋዎን ፣ ቦርፎሪከን ፣ የሚባሉ ፡ አሉና ፤ አንድም ፡ ከፀሐይ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበረ ፡ አካላዊ ፡ ቃልን ፡ ያመሰግኑታል ፤

ወይሴብሕዎ ፡ በጥበብ ፤

በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እየተቃኙ ፤

፲፪ ፤ ወይጠበቡ ፡ በነገር ፤

በነገር ፡ እየተራቀቁ ፣ ባንድነቱ ፡ ምንታዌ ፤ በሦስትነቱ ፡ ርባዔ ፡ ሳይጨምሩ ፤

ወበመንፈስ ፡ ሕይወት ፤

ሕይወት ፡ በሚሆን ፡ በመንፈስ ቅዱስ ፡ እየተቃኙ ፡ ያመሰግናሉ ፤

ወእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፡ አንበሮ ፡ ለኅሩይ ፤

የማሕፀኑን ፡ መልሶ ፡ መናገር ፡ ነው ፤ የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ክርስቶስን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ አስቀመጠው ፤

፲፫ ፤ ወይኬንን ፡ ኵሎ ፡ ግብሮሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ በመልዕልተ ፡ ሰማያት ፤

ጻድቃን ፡ የሠሩትን ፡ ሥራ ፡ አውቆ ፡ በሰማይ ፡ ይፈርዳል ፤

ወበመዳልው ፡ ይደለው ፡ ምግባሮሙ ለኵሎሙ ፤

ሥራቸው ፡ በፍትሐ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመረመራል ፤

፲፬ ፤ ወሶበ ፡ ያሌዕል ፡ ገጾ ፡ ከመ ፡ ይኰንን ፡ ፍኖቶሙ ፡ እንተ ፡ ኅቡዕት በነገረ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

በስሙ ፡ እምነው ፡ ሰውረው ፡ የሠሩትን ፡ ሥራ ፡ አውቆ ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ አንገቱን ፡ ባቀና ፡ ጊዜ ፤

ወአሠረ ፡ ዚአሆሙ ፡ በፍኖተ ፡ ኵነኔ ጽድቅ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ ልዑል ፤

በልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ በእውነተኛ ፡ ሕግ ፡ ፀንተው ፡ የሠሩትን ፡ አውቆ ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ አንገቱን ፡ ባቀና ፡ ጊዜ ፤

፲፭ ፤ ይትናገሩ ፡ ኵሎሙ ፡ በ፩ዱ ፡ ቃል ፤

ሁሉም ፡ በአንድ ፡ ቃል ፡ ያመሰግናሉ ፤

ወይባርኩ ፡ ወይሴብሑ ፡ ወያሌዕሉ ፡ ወይዌድሱ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ ፤ የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስምንም ፡ ያከብራሉ ፤ ያመሰግናሉ ፤

፲፮ ፤ ወይጼውዕ ፡ ኵሎ ፡ ኃይለ ፡ ሰማያት ፡ ወኵሎሙ ፡ ቅዱሳን ፡ ዘመልዕልት ፤

---

፩ ፤ ያዕቆብ ፡ ፫ ፡ ፲፯

ሠራዊተ ፡ መላእክትን ፤ ሊቃነ፡ መላእክትን ፡ ለምስጋና ፡ ይጠራል ፤

፲፯ ፤ ወኃይለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኪሩቤል ፡ ወሱራፌል ፡ ወአፍኒን ፡ ወኵሎሙ ፡ መላእክተ ፡ ኃይል ፤

የእግዚአብሔር ፡ ሠራዊት ፡ ኪሩቤል ፤ ሱራፌል ፤ አፍኒን ፤ እሊህ ፡ እውቀት ፡ ያላቸው ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑታል ፤

ወኵሎሙ ፡ መላእክተ ፡ አጋዕዝት ፤

ሥላሴ ፡ የፈጠሯቸው ፤ አንድም ፡ ሥላሴን ፡ የሚያመሰግኑ ፤ የሚያገለግሉ ፤

ወኅሩይ ፤

መላእክተ፡ ኅሩይ ፡ ሲል ፡ ነው፤ ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ የፈጠራቸውን፡ አንድም ፡ ክርስቶስን ፡ የሚያገለግሉ ፡ መላእክት ፡ ያመሰግኑታል ፤ ፬ኛ ፡ ማለት ፡ አይደለም ፡ በመለኮቱ ፡ እንዲያመሰግኑት ፤ በሰውነቱም ፡ ያመሰግኑታል ፡ ሲል ፡ ነው ፤

ወካልእ ፡ ኃይል ፤

ሌላ ፡ ዕውቀትም ፡ ይሰጣል ፤ ካልእ ፡ ከመላእክት ፡ ልዩ ፡ የሚሆኑ ፤

፲፰ ፤ እለ ፡ ውስተ ፡ የብስ ፡ ዲበ ፡ ማይ ፤

በውኃ ፡ ላይ ፡ በጸናች ፡ በዚህች ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ ጻድቃን ፡ ያመሰግኑታል ፤

በይእቲ ፡ ዕለት ፡ ይነሥኡ ፡ ፩ደ ፡ ቃለ ፡ ወይባርኩ ፤ ወይሴብሑ ፡ ወይዌድሱ ፡ ወያሌዕሉ ፡ በመንፈሰ ፡ ሃይማኖት ፤

ሃይማኖት ፡ በያዘ ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ ሃይማኖትን ፡ በሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

ወበመንፈሰ ፡ ጥበብ ፤

ጥበብ ፡ ባለው ፡ ልቡና ፤ አንድም፡ ጥበብን ፡ በሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

ወበትዕግሥት ፤

ትዕግሥት ፡ ባለው ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ ትእግሥትን ፡ በሚያሳድር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

፲፱ ፤ ወበመንፈሰ ፡ ምሕረት ፤

ምሕረት ፡ ባለው ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ ምሕረትን ፡ በሚያሳድር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

ወበመንፈሰ ፡ ኰነኔ ፤

ፍርድን ፡ በሚያውቅ ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ ፍርድን ፡ በሚገልጽ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

ወሰላም ፤

ፍቅር ፡ ባለው ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ ፍቅርን ፡ በሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤

ወበመንፈሰ ፡ ኂሩት ፤

በጐነት ፡ ባለው ፡ ልቡና ፤ አንድም ፡ በጐነትን ፡ በሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጻድቃን ፡ ይባርካሉ ፤ ያከብራሉ ፤ ያመሰግናሉ ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋሉ ፤

፳ ፤ ወይብሉ ፡ ኵሎሙ ፡ በ፩ዱ ፡ ቃል ፡ ቡሩክ ፤
ሁሉም ፡ ባንድ ፡ ቃል ፡ የከበረ ነው ፤
ወይትባረክ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለም ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስሙም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ይክበር ፡ ይመስገን ይላሉ ፤
፳፩ ፤ ወእስከ ፡ ለዓለም ፡ ይባርክዎ ፡ ኵሎሙ ፡ ቅዱሳን ፡ እለ ፡ ኢይነውሙ ፡ በመልዕልተ ፡ ሰማያት ፤
የማያርፉ ፤ በሰማይ ፡ ያሉ ፤ መላእክትም ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ ያመሰግኑ ታል ፤
ይባርክዎ ፡ ኵሎሙ ፡ ቅዱሳኑ ፡ እለ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፤
በልዕልና ፡ ያሉ ፡ ሕጋውያን ፡ ሁሉ ፤
ወኵሎሙ ፡ ኅሩያን ፡ እለ ፡ የኀድሩ ውስተ ፡ ገነተ ፡ ሕይወት ፡
ሕይወተ ፡ ነፍስ ፡ በሚገኝበት ፡ በገነት ፡ የሚኖሩ ፡ ደናግል ፡ ያመሰግናሉ ፤
፳፪ ፤ ወኵሉ ፡ መንፈሰ ፡ ብርሃን ፡ ዘትክል ፡ ባርኮቶ ፡ ወሰብሖቶ ፡ ወአል ዕሎቶ ፤
ወኵላ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በውስጥ በአፍኣ ፡ እርሱን ፡ ማመስገን ፡ የምትችል ፡ ዕውቀት ያላት ፡ ልቡና ፡ ናት ፤ አንድም ፡ ዕውቀት ፡ ያላት ፡ ልቡና ፡ እርሱን ፡ በውስጥ ፡ በአፍዓ ፡ ማመስገን ፡ የሚቻላት ፡ ናት ፤
ወቀድሶቶ ፡ ለስምከ ፡ ቅዱስ ፤
ለስምህ ፡ ምስጋና ፡ ማቅረብ ፡ የሚቻላት ፡ ዕውቀት ፡ ያላት ፡ ልቡና ፡ ናት ፤
፳፫ ፤ ወኵሉ ፡ ዘሥጋ ፡ ዘፈድፈደ ፡ እምኃይል ፡ ትሴብሕ ፡ ወትባርክ ፡ ለስ ምከ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ወኵላ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ሥጋዊት፣ ደማዊት ፤ ሰውነት ፡ ሁላ ፡ ከልክ፡ የወጣ ፡ ምስጋናን ፡ ለዘላለሙ ፡ ታመሰግናለች ፤ አንድም ፡ በዕ ውቀት ፡ ታመሰግናለች ፤
እስመ ፡ ብዙኀ ፡ ምሕረቱ ፡ ለእግዚአ፡ መናፍስት ፡ ወርኁቀ ፡ መዓት ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ቸርነቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፤ ከቁጣም ፡ የራቀ ፡ ነውና፤
ሥጋዊት ፡ ደማዊት ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ከዕውቀት ፡ የወጣ ፡ ምስ ጋና ፡ ፈጽማ ፡ ታቀርባለች ፤
፳፬ ፤ ወኵሉ ፡ ግብሮ ፡ ወኵሉ ፡ ኃይሉ ፡ በአምጣነ ፡ ገብረ ፤ ከሠተ ለጻድቃን ፡ ወለኅሩያን ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ሥራውን ፡ ሁሉ ፤ ያደረገውንም፡ ኃይል ፡ ሁሉ ፤ በመላእክት ፡ ጌታ፡ ስም ፡ ላመኑ ፡ ለደናግልና ፡ ለሕጋውያን ፡ ገለጸ፤
፳፭ ፤ ወከመዝ ፡ አዘዘ ፡ እግዚአ ፡ ለነገሥት ፤ ወለአዚዛን ፤ ወለልዑላን ፤

ወለኃያላን ፣ ወለአለ ፡ የኀድርዋ ፡ ለምድር ፤
ገዥ ፡የሚሆን ፡ ጌታም ፡ በዚህ፡ ዓለም ፡ ለሚኖሩት ፡ ለኃያላን ፣ ለጽኑዓን ፣ ለልዑላን ፣ ነገሥታት ፡ እንዲህ ፡ እንዲህ ፡ እድርጎ ፡ አዘዘ ፤
፳፮ ፤ ወይብል ፡ ክሥቱ ፡ አዕይንቲ ክሙ ፤
ዓይነ ፡ ልቦናችሁን ፡ ግለጡ ፤
ወአንሥኡ ፡ አቅርንቲክሙ ፤
ሥልጣናችሁን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጉ ፤
እመ ፡ ትክሉ ፡ አእምሮቶ ፡ ለኅሩይ፤
ኅሩይ ፡ ክርስቶስን ፡ ማወቅ ፡ ይቻላችሁ ፡ እንደሆነ ፡ አለ ፤
፳፯ ፤ ወነበረ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤
እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ክርስቶስ በዙፋኑ ፡ (በጌትነት) ፡ተቀመጠ፤
ወመንፈስ፡ ጽድቅ ፡ ተክዕወ፡ ዲቤሁ፣
የባሕርይ ፡ ሕይወቱ ፡ መንፈስ ቅዱስ ፡ በእርሱ ፡ ተገለጸ ፤ የማ ሕፀኑን ፡ መልሶ ፡ መናገር ፡ ነው ፤
፳፰ ፤ ወነገረ ፡ አፉሁ ፡ ይቀትል ፡ ኵሉ ፡ ኃጥአነ ፤
ሑሩ ፡ እምኔየ ፡ ያለው ፡ ቃሉ ኃጥአንን ፡ ያጠፋል ፤
ወኵሉ ፡ ዓማፅያነ ፡ ወእምገጹ ፡ ይትኀጐሉ ፤
በደለኞችንም ፡ ሁሉ ፡ ይገድላል ፤
ማለት፡ ሑሩ ፡ እምኔየ፡ይላል ፤
እነርሱም ፡ ከፊቱ ፡ ይጠፋሉ ፤

፳፱ ፤ ወይቀውሙ ፡ በይእቲ፡ ዕለት ፡ ኵሎሙ ፡ ነገሥት ፡ ወአዚዛን ፣ ወልዑላን ፣ ወእለ ፡ ይእኀዝዋ ፡ ለምድር ፤
በዚያችም ፡ ቀን ፡ ነገሥታቱ ፣ ሁሉ ፡ የከበሩ ፡ ሰዎችና ፡ የጸኑ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ይህችንም ፡ ዓለም ፡ የሚገዙዋት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይቆማሉ ፤
፴ ፤ ወይሬእይዎ ፡ ወየአምርዎ ፡ ከመ ፡ ይነብር ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብ ሐቲሁ ፤
በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ተቀምጦ ፡ ያዩታል ፤ ያውቁታል ፤
ወጻድቃን ፡ በጽድቅ ፡ ቅድሜሁ ፡ ይትኬነኑ ፤
ጻድቃን ፡ በፊቱ ፡ ይፈረድላቸ ዋል ፤
፴፩ ፤ ወነገረ ፡ በከ ፡ አልቦ ፡ ዘይት በሀል ፡ በቅድሜሁ ፤
በፊቱ ፡ ዋዛ ፡ ዘበሬታ ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ የለም ፤
፴፪ ፤ ወይመጽእ ፡ ዲቤሆሙ ፡ ሕማም ፡ ከመ ፡ ብእሲት ፡ እንተ ውስተ ፡ ማሕምም ፤
በምጥ ፡ እንደ ፡ ተያዘች ፡ ሴት በኃጥአን ፡ ላይ ፡ ጭንቅ ፣ መከራ ፡ ይመጣባቸዋል ፤
ወየዐጽባ ፡ ወሊድ ፡ ሶበ ፡ ይመጽእ ፡ ወልዳ ፡ በአፈ ፡ ማሕፀና ፤
ልጁ ፡ ከማሕፀኗ ፡ ሊወጣ ፡ በመጣ፡ ጊዜ ፡ ምጡ፡ ጭንቅ ፡ እንዲሆንባት ፤

ወተዓፅበ ፡ ለወሊድ ፤
በምጡ ፡ እንድትጨነቅ ፡ ይጨነ
ቃሉ ፤
፴፫ ፤ ወይሬእይዎሙ ፡ መንፈቆሙ ፡ ለመንፈቆሙ ፤
እኩሌቶቹ ፡ ኃጥእን ፣ እኩሌቶቹ፡ ኃጥእንን ፡ ያይዋቸዋል ፤ አን ድም ፡ ኃጥእን ፡ ጻድቃንን ፡ ያያሉ ፤ ወመንፈቆሙ ፣ ያልተካ ከለ ፡ ነው ፤ ንፍቃ ፡ ለዕለት ፡ ወመንፈቆሙ ፡ ኗፊቁ ፡ እንዳ ለው ፡ ያለ ፡ ነው ፤
ወይደነግፁ ፡ ወያቴሕቱ ፡ ገጾሙ ፤
ኃጥእን ፡ ይደነግጣሉ ፤ አንገታ ቸውን ፡ ይደፋሉ ፤
፴፬ ፤ ወይእኀዞሙ ፡ ሕማም፡ ሶበ ፡ ይሬእይዎ ፡ ለዝኩ ፡ ወልደ ፡ ብእሲት እንዘ ፡ ይነብር ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤
ወልደ፡ ክርስቶስሃ፡ሲል ፡ ነው፣ ወልደ ፡ ብእሲት ፡ ከድንግል ፡ የተወለደ ፡ ያንን ፡ ክርስቶስን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ተቀምጦ ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡ መከራው ፡ እስ ጨንቆ ፡ ይይዛቸዋል ፤
፴፭ ፤ ወይሴብሕዎ ፡ ወይባርክዎ ፡ ወያሌዕልዎ ፡ ነገሥት ፡ እዚዛን ፤
የአዳም ፡ ልጅ ፡ ክርስቶስ ፡ ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ በሥጋ ፡ አልተገለ ጠም ፡ ነበርና ፡ የጸኑ ነገሥታት ፤
ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይእኀዝዋ ፡ ለም ድር ፡ ለዘይመልክ ፡ ኵሎ ፡ ዘኅቡዕ ፤
ይህችን፡ዓለም፡የሚገዙ ፡ ሁሉ ፣ ረቂቃን ፡ ፍጥረታትን ፡ ሁሉ ፡ የሚገዛ ፡ ጌታን ፡ ያመሰግናሉ ፤
፴፮ ፤ እስመ ፡ እምቅድም ፡ ኅቡዓ ፡ ኮነ ፡ ወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፤
ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ክርስቶስ ፡ የተሰወረ ፡ ነበርና ፤
ወዐቀቦ ፡ ልዑል ፡ በቅድመ ፡ ኃይሉ ፡ ወከሠቶ ፡ ለኅሩያን ፤
ለሐዋርያት ፣ ለምዕመናን ፣ በዘ መነ ፡ ሥጋዌው ፡ ገለጸው ፤
ወይዘራዕ ፡ ማኅበረ ፡ ቅዱሳን ፡ ወኅሩያን ፤
የሐዋርያት ፡ ጉባዔ ፡ ይሰፋል ፤ አንድም ፡ እስመ ፡ እምቅድም ፡ የጌታ ፡ ነገሩ ፡ ተሰውሮ ፡ ነበ ርና ፤
ወዐቀቦ ፤ በመላእክት ፡ ፊት ፡ አጸናው ፤ በሥጋዌ ፣ በምጽአት ፣ መላእክት ፡ እንዲያውቁት ፡ አደ ረገ ፣ ወከሠቶ ፤ ለደናግል ፣ ለሕ ጋውያን ፣ በምጽአት ፡ ገለጸው ፤
ወይዘራዕ ፣ የሕጋውያን ፡ የደና ግል ፡ ወገን ፡ ጉባኤያቸው ፡ ይሰ ፋል ፤
፴፯ ፤ ወይቀውሙ ፡ በቅድሜሁ ፡ ኵሎሙ ፡ ኅሩያን ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፣
ወዳጆቹ ፡ ጻድቃን ፡ ሁሉ ፡ በዚ ያች ፡ ቀን ፡ በፊቱ ፡ ይቆማሉ ፤

፰ ፡ ወይወድቁ ፡ ኵሎሙ ፡ ነገ
ሥት ፡ አዚዛን ፡ ወልዑላን ፤
ነገሥታቱ ፣ ኃያላኑ ፡ ሁሉ ፡
በዚያች ፡ ቀን ፡ በፊቱ ፡ ይወድ
ቃሉ ፤
ወእለ ፡ ይመልክዋ ፡ ለየብስ ፣
ይህችን ፡ ዓለም ፡ የሚገዟት ፡
ሰዎችም ፡ ሁሉ ፣
በቅድሜሁ ፡ በገጸሙ ፡ ወይሰግዱ ፤
እግር ፡ ከግንባር ፡ አድርገው ፡
በፊቱ ፡ ወድቀው ፡ ይሰግዳሉ ፤
፱ ፡ ወይሴፈውዎ ፡ ለዝኩ ፡ ወልደ ፡
ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ወያስተበቍዕዎ ፤
ያን ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ክርስ
ቶስንም ፡ ተስፋ ፡ ያደርጉታል ፡
ይማለዱታል ፤
ወይስእሉ ፡ ምሕረተ ፡ እምኀቤሁ ፣
ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ይቅርታን ፡
ይለምናሉ ፤
፲ ፡ ወያጌጕእሙ ፡ እንከ ፡ ውእቱ ፡
እግዚእ ፡ መናፍስት ፡ ከመ ፡ ያፍጥኑ፡
ወይፃኡ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ፤
ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ያ ፡ የመላእክት
ጌታ፡ ከፊቱ ፡ ፈጥነው ፡ ይወጡ
ዘንድ ፡ ያስቸኵላቸዋል ፤
፲፩ ፡ ወገጸሙ ፡ ይመልዕ ፡ ኃፍረተ ፤
ፊታቸውም ፡ ኀፍረትን ፡ ይመላል ፤
ወጽልመት ፡ ይትዌሰክ ፡ ገጸሙ ፤
ፊታቸው ፡ በጨለማ ፡ ላይ ፡
ጨለማን ፡ ይጨምራል ፤

፲፪ ፡ ወይትሜጠውዎሙ ፡ መላእ
ክተ ፡ መቅሠፍት ፤
ለመቅሰፍት ፡ የታዘዙ ፡ መላእ
ክት ፡ ይቀበሏቸዋል ፤
ከመ ፡ ይትፈደዩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘገፍ
ዕዎሙ ፡ ለደቂቁ ፡ ወለኅሩያን ፡
ዚአሁ ፤
ልጆች ፡ ደናግልን ፣ ሕጋውያ
ንን ፡ ከበደሏቸው ፡ ፍዳ ፡ ይከ
ፍሏቸው ፡ ዘንድ ፤ እንድም
በእነርሱ ፡ ፍዳ ፡ ያጸኑባቸው ፡
ዘንድ ፤
፲፫ ፡ ወይከውኑ ፡ አርአያ ፡ ለኅሩያ
ኒሁ ፤
ኃጥአን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለጻድ
ቃን ፡ አብነት ፡ ይሆናሉ ፤ እነ
ሱን ፡ ሲያጠፏቸው ፡ አይተው፡
ጻድቃን ፡ ይመለሳሉና ፤
፲፬ ፡ ወጻድቃን ፡ ዚአሁ ፡ በሙ ፡
ይትፌሥሑ ፤
ወዳጆቹ ፡ በእነርሱ ፡ ጥፋት ፡
ደስ፡ ይላቸዋል ፡ አለ ፤ በኃጥአን ፡
ጥፋት ፡ ደስ ፡ የሚላቸው ፡ ሁነው ፡
አይደለም ፤ ፍርዱ ፡ ስላልቀረ ፡
ነው ፤
እስመ ፡ መዓቱ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍ
ስት ፡ ዲቤሆሙ ፡ ተአርፍ ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ቍጣው ፡
በእነርሱ ፡ ትጸናለች ፤
ወመጥባሕቱ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፤
ትሰክር ፡ እምኔሆሙ ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ሾተሉም ፡ ከደማቸው ፡ የተነሣ ፡ ትስክራ ለች ፡ አለ ፤ ደማቸውን ፡ ታፈሳ ለች ፤ አንድም ፡ ሥልጣኑ ፡ ታጠ ፋቸዋለች ፤

፵፭ ፤ ወጻድቃን ፡ ወኅሩያን ፡ ይድኅኑ ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፤

ደናግልና ፡ ሕጋውያኑም ፡ በዚ ያች ፡ ቀን ፡ ይድናሉ ፤

፵፮ ፤ ወገጸሙ ፡ ለኃጥአን ፡ ወለ ዓማፅያን ፡ ኢይሬእዩ ፡ እምይእዜ ፤

ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የበደለኞች ንና ፡ የኃጥአንን ፡ ፊት ፡ አያዩም ፤

ወእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ዲቤሆሙ ፡ የዓርፍ ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ጻድቃንን ፡ ተዋሕዷቸው ፡ ይኖራሉ ፤

፵፯ ፤ ወምስለ ፡ ዝኩ ፡ ወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ የኀድሩ ፡ ይበልዑ ፡ ወይሰትዩ ፡ ወይሰክቡ ፤

የሚበሉ ፣ የሚጠጡ ፣ የሚተኙ ፣ የሚነሱ ፡ ሁነው ፡ አይደለም ፤ በልቶ ፡ ጠጥቶ ፡ ተኝቶ ፡ የተ ነሣ ፡ ደስ ፡ እንዲለው ፡ ደስ ፡ ይላ ቸዋል ፡ ሲል ፡ ነው ፤

ወይትነሥኡ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

ለዘለዓለሙም ፡ ይከብራሉ ፤

፵፰ ፤ ወተንሥኡ ፡ ጻድቃን ፡ ወኅሩ ያን ፡ እምድር ፤

ደናግልና ፡ ሕጋውያን ፡ ከኃሣር ፡ ከመከራ ፡ ተነሡ ፤

ወነደጉ ፡ አትሕቶ ፡ ገጸሙ ፤

አንገታቸውን ፡ መስበር ፡ ተዉ ፤

፵፱ ፤ ወለብሱ ፡ ልብሰ ፡ ሕይወት ፤

ልብስ ፡ ግሥ ፡ ነው ፤ ሕይወትን ፡ ገንዘብ ፡ አደረጉ ፤ አንድም ፡ ልብሰ ፡ ሕይወት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ለበሱ ፤

ወውእቱ ፡ ይከውን ፡ ልብሰ ፡ ሕይወት ፡ በኀበ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤

ሕይወታቸው ፤ አንድም ፡ ልብሰ ፡ ሕይወት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ዘንድ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤

፶ ፤ ወአልባሲክሙ ፡ ኢይበልዩ ፡ ወስ ብሐቲክሙ ፡ ኢየሐልቅ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤

ልብሳችሁ ፡ አያልቅ ፣ ክብራችሁ ፡ አያልፍ ፣ ምን ፡ ያምርባችሁ ? አልባሲሆሙ ፡ ቢል ፣ ልብሳቸው ፡ አያልቅ ፡ ክብራቸው ፡ አያልፍ ፣ ምን ፡ ያምርባቸው ? በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ አያልቅም ።

፶፩ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ያስ ተበቍዑ ፡ ነገሥት ፡ አዚዛን ፡ እለ ፡ ይእኅዝዋ ፡ ለየብስ ፡ እመላእክተ ፡ መቅ ሠፍት ፡ በኀበ ፡ ሀሎዉ ፡ ምጥዋነ ፡ ከመ ፡ የሀብዎሙ ፡ ዕረፍተ ፡ ንስቲተ ፤

ለጻድቃን ፡ ፈርዶ ፡ መንግሥተ ሰማያትን ፡ ባወረሳቸው ፡ ጊዜ ፣ በኃጥአን ፡ ፈርዶ ፡ ገሐነመ ፡ እሳት ፡ ባወረዳቸው ፡ ጊዜ ፣ ይህ ችን ፡ ዓለም ፡ የሚገዟት ፣ የጸኑ ፡ ነገሥታቱ ፡ ከመላእክተ ፡ መቅ

ሠፍት ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ በተ
ጋዙበት ፡ ቦታ ፡ ዕረፍት ፡ ይሰ
ጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ይማልዳሉ ፤
ወከመ ፡ ይደቁ ፡ ወይስግዱ ፡ በቅድመ
እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ይወ
ድቁ ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፤
፶፪ ፤ ወይትአመኑ ፡ ኃጢአቶሙ ፡
በቅድሜሁ ፤
ክፉ ፡ ነን ፡ ጥፉ ፡ ነን ፣ ብለው
ኃጢአታቸውን ፡ ያምኑ ፡ ዘንድ
ጥቂት ፡ ዕረፍት ፡ ሊሰጧቸው፡
ከመላእክተ ፡ መቅሠፍት ፡ አን
ዱንም ፡ አንዱን ፡ ይማልዳሉ፤
ወይባርክዎ ፡ ወይሴብሕዎ ፡ ለእግዚአ
መናፍስት ፤
ይህን ፡ አይተው ፡ የመላእክትን
ጌታ ፡ ፈጽመው ፡ ያመሰግኑታል ፤
፶፫ ፤ ወይብሉ ፡ ቡሩክ ፡ ውእቱ ፡
እግዚእ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡
ወእግዚአ ፡ ነገሥት ፤
ነገሥታቱን ፡ የሚገዛ ፡ የነገሥ
ታቱን ፡ መንግሥት ፡ የሚያሳ
ልፍ ፣
እግዚኦሙ ፡ ለአዚዛን ፤
ኃያላኑን ፡ የፈጠረ ፡ የሚገዛ ፡
የኃያላኑን ፡ ኃይል ፡ የሚያጠፋ፣
ወእግዚኦ ፡ ለባዕል፤
ባለጸጋውን ፡ የፈጠረ ፡ የሚገዛ
ባለጸጋውን ፡ ከብዕሉ ፡ (ከሀብቱ)
የሚለይ ፤

ወእግዚአ ፡ ስብሐት ፤
የክብር ፡ ባለቤት ፣
ወእግዚአ ፡ ጥበብ ፤
ጥበብን ፡ የሚገልጽ ፣ የእውቀት ፡
ባለቤት ፣
ወይበርህ ፡ ቦቱ ፡ ኵሉ ፡ ኅቡዕ ፤
የተሰወረው ፡ ምሥጢር ፡ ሁሉ ፡
የሚገለጽበት ፤
፶፬ ፤ ወኃይልከ ፡ ለትውልደ ፡ ትው
ልድ ፤
ኃይልህ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡
እያሉ ፡ ያመሰግኑታል ፤
ወስብሐቲከ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ጌትነትህም ፡ ለዘለዓለም ፡ ነው ፤
፶፭ ፤ ዕሙቅ ፡ ውእቱ ፡ ኅቡዓት ፡
ዚአከ ፡ ኵሉ ፤
ያንተ ፡ ምሥጢር ፡ ረቂቅ ፡ ነው ፤
ወኍልቍ ፡ አልቦ ፤
ለጥበብህ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የለ
ውም ፤
ወለጽድቅ ፡ ዚአከ ፡ ሐሣብ ፡ አልቦ ፤
ለአንተ ፡ ቸርነት ፡ ሥፍር ፡ ቍጥር ፡
የለውም ፤ አንድም ፡ አይመረ
መርም ፤ እያሉ ፡ መላእክት ፡
ያመሰግናሉ ፤
፶፮ ፤ ይእዜኒ ፡ አእመርነ ፡ ከመ ፡
ንሰብሕ ፡ ወንባርክ ፡ ለእግዚአ ፡ ነገ
ሥት ፤
ኃጥአንም ፡ የነገሥታቱን ፡ ጌታ፡
እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡
አወቅን ፡ ይላሉ ፤

ወለዘይነግሥ ፡ ዲበ ፡ ኵሉሙ ፡ ነገሥት ።
በነገሥታቱ ፡ ሁሉ ፡ መንግሥ ቱን ፡ የገለጸ ፡ ጌታን ፡ እናመ ሰግነው ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ አወቅን ይላሉ ፡ ኃጥአን ።
፶፮ ፤ ወይቤሉ ፡ መኑ ፡ እምወሀበነ ፡ ዕረፍተ ፡ ከመ ፡ ንሰብሖ ፡ ወናእኵቶ ፡ ወንባርኮ።
በአፍአ ፡ በውስጥ ፡ እናመሰግ ነው ፡ ዘንድ ፡ ዕረፍትን ፡ ማን ፡ በሰጠን ? ይላሉ ፣ ኃጥአን ፡ ገጸ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙምና ፤
ወንእመን ፡ ቅድመ ፡ ስብሐቲሁ ፤ በጌትነቱ ፡ ፊት ፡ እናምን ፡ ዘንድ፡ ዕረፍትን ፡ ማን ፡ በሰጠን? ይላሉ፣ ነገር ፡ ግን ፡ ገጸ ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙም ፤
፶፯ ፤ ወይእዜኒ ፡ ዕረፍተ ፡ ንስቲተ ፡ ንትሜነይ ፤
አሁንም ፡ ጥቂት ፡ ዕረፍትን ፡ እንመኛለን ፤
ወኢንረክብ ፤
አናገኝም ፡ ይላሉ ፤ ገጸ ፡ ፍት ሑን ፡ አያገኙም ፤
ንስደድዲ ፡ ወኢንእኅዝ ፤
ከተድላ ፡ በመከራ ፡ እንሰደዳለን የሚያድነን ፡ የለም ፣ ከክፉ ፡ ቦታ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ የሚይዘውን ቢአገኝ ፡ ያነን ፡ ተጠግቶ ፡ እን ዲድን ፡ ጥግ ፡ ይዘን ፡ እንቀ ርም ፡ አለ ፣ የሚያድን ፡ የለም ፤

፶፱ ፤ ወብርሃን ፡ እምቅድሜነ ፡ ኀለፈ ፤
ተድላ ፡ ደስታችን ፡ ከእኛ ፡ ጠፋ፤
ወጽልመት ፡ ምንባሪነ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ለዘለዓለሙም ፡ መኖሪያችን ፡ ጨለማ ፡ ነው ፡ ይላሉ ፤ ገጸ ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙምና ፤
እስመ ፡ በቅድሜሁ ፡ ኢአመነ ፡ ወኢሰ ባሕነ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፤
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ አም ነን ፤ አንድም ፡ ስሙን ፡ አምነን ፡ አላመሰገነውምና ፤
፷ ፤ ወኢሰባሕናሁ ፡ ለእግዚእ ፡ በኵሉ ፡ ተግባሩ ፤
በሥራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉም ፡ ጌታን ፡ አላመሰገንነውም ፤
ወተስፋነ ፡ ከነ ፡ ዲበ ፡ በትረ ፡ መንበረ ፡ መንግሥትነ ፤
በትር ፡ መንበር ፡ አንድ ፡ ወገን ፣ አለኝታችንም ፡ በመንግሥታችን፡ ዙፋን ፡ ሥልጣን ፡ ሆነ ፤ አን ድም ፣ ቀድሞ ፡ ጌታችን ፡ የመን ግሥታችን ፡ ሥልጣን ፡ አለኝታ ችን ፡ ነበርና ፡ መኖሪያችን ፡ ነው ፡ ይላሉ ፣ ገጸ ፡ ፍትሑን፡ አያገኙም ፤
፷፩ ፤ ወስብሐቲነ ፡ በዕለተ ፡ ሥራኅነ፡ ወምንዳቤነ ፤
በጭንቅ ፡ መከራችን ፣ በጸዋትወ መከራችን ፡ ጊዜ ፤

ኢያድኅነነ ፤
ይህ ፡ ሥልጣናችን ፡ አያድነንም ፡ ይላሉ ፤ ገጸ ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙም ፤
፰፱ ፤ ወኢንረክብ ፡ ዕረፍተ ፡ ንእመን ፤
እናምን ፡ ዘንድ ፡ ዕረፍትን ፡ እናገኝም ፡ ይላሉ ፤ ገጸ ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙም ፤
እስመ ፡ መሐይምን ፡ ውእቱ ፡ እግዚእነ ፡ በኲሉ ፡ ምግባሩ ፡ ወበኲሉ ፡ ኰነኔሁ ፡ ወጽድቁ ፤
ጌታችን ፡ እግዚአብሔርም ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ በቸርነቱና ፡ በፍርዱ ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነውና፤
፰፲ ፤ ወገጸ ፡ ኰነኔሁ ፡ ኢይነሥኡ፤
ገጸ ፡ ፍትሑን ፡ አያገኙም ፤
ወነኀልፍ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ በእንተ ፡ ምግባሪነ ፤
በሠራነው ፡ ኃጢአታችን ፡ ተፈርዶብን ፡ ከፊቱ ፡ እንሄዳለን ፤
ወኲሉ ፡ ኃጢአትነ ፡ በጽድቅ ፤ ተኈለቈ ፡ ኃጢአታችንም ፡ ሁሉ ፡ በእውነት ፡ ተቈጠረ፤
፰፲፩ ፤ ወይእዜኒ ፡ ይብልዎሙ ፡ ትጽግብ ፡ ነፍስነ ፡ እምንዋየ ፡ ዓመፃ ፤
እንዲህ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ ሳለባቸው ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰርቀን ፡ ቀምተን ፡ ካጠራቀምነው፡ ከብት ፡ ሰውነታችን ፡ ትጥገብ ፡ ይላሉ ፤ ትጸግብ ፡ ቢል ፡ ትጠግባለች ፡ ይላሉ ፤

ወኢትከልዕ ፡ ወሪዶተነ ፡ እምላህባ ፡ ለክበደ ፡ሲኦል ፤
እምክቡድ ፡ ሲኦል ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ይህ ፡ አለመብላታችን ፡ አለመጠጣታችን ፡ ጭንቅ ፡ ወደሆነች ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ከመውረድ ፡ አትከለክለንምና ፡ ዛሬ ፡ ሰውነታችን ትጥገብ ፡ ይላሉ ፤
፰፲፪ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ይመልዕ ፡ ገጸሙ ፡ ጽልመተ ፤
ሑሩ ፡ ካላቸው ፡ በኋላ ፡ ፊታቸው ፡ ጨለማን ፡ ይመላል ፤
ወኃፍረተ ፡ በቅድመ ፡ ዝኩ ፡ ወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፤
በወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ክርስቶስ ፡ ፊት ፡ በአዳም ፡ ልጅ ፡ ኃፍረትን ፤ ይሞላሉ ፤
፰፲፫ ፤ ወእምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ይሰደዱ ፤
ከፊቱም ፡ ተሰድደው ፡ ይሄዳሉ፤
ወሰይፍ ፡ ዩነድር ፡ ቅድመ ፡ ገጹ ፡ ማዕከሎሙ ፤
በኃጥአንና ፡ በጻድቃን ፡ መካከል ሰይፍ ፡ ይመዘዛል ፡ አለ ፤ ጻድቃንንና ፡ ኃጥአንን ፡ የሚለይ ፡ ሥልጣን ፡ በፊቱ ፡ ይገለጻል ፤
፰፲፬ ፤ ወከመዝ ፡ ይቤ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ሥርዓቶሙ ፤
ለጻድቃን ፡ የሚፈርድላቸው ፤
ወኰነኔሆሙ ፡ ለእዚዛን ፤

በኃጥአን ፡ የሚፈርድባቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ፡ የመላእክት ጌታ ።
ወሰነገሥት ፡ ወለልዑላን ፡ ወለእለ ፡ ይእኀዝዋ ፡ ለየብስ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ።
ይህችን ፡ ዓለም ፡ የያዟት ፡ የሚገዟት ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ሥራቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ።
፳፰ ፤ ወካልዓተ ፡ ገጸተ ፡ ርኢኩ ፡ በውእቱ ፡ መካን ፡ ኅቡዓተ ።
ይህን ፡ የተሠወረውን ፡ ምሥጢር ፡ ባየሁበት ፡ ቦታ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎች ፡ አየሁ ።
፳፱ ፤ ወሰማዕኩ ፡ ቃሎ ፡ ለመልአክ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ እሉ ፡ እሙንቱ ፡ መላእክት ፡ እለ ፡ ወረዱ ፡ እምሰማይ ዲበ ፡ ምድር ።
ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ ከልዑል ፡ መዓርግ ፡ ከሰማያዊ ፡ ግብር ፡ የወረዱ ፡ እሊህ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ናቸው ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ ሰማሁ ፡
ወዘበኀቡዕ፡ ከሠቱ ፡ ለውሉደ፡ ሰብእ ።
የተሠወረውን ፡ ምሥጢረ ፡ ኃጣውእን ፤ ምሥጢረ ፡ አጋንንትን ለሰው ፡ ልጆች ፡ የገለጹ ።
ወአስሐትምሙ ፡ ለውሉደ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ይግበሩ ፡ ኃጢአተ ።
ኃጢአት ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ የቃየልን ፡ ልጆች ፡ ያሳቷቸው ፡ መላእክት ፡ እሊህ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ናቸው ፡ ሲል ፡ የመልአኩን ፡ ቃል ፡ ሰማሁ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፲፰ ።

### ጉባኤ

፩ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ርእየ ፡ ኖኅ ፡ ከመ ፡ አጽነነት ፡ ምድር ።
ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ከደብር ፡ ቅዱስ ወርደው ፡ ኃጢአት ፡ በሠሩበት ወራት ፤ ምድር ፡ ለጥፋት ፡ እንደቀረበች ፡ ኖኅ ፡ አየ ፤ አንድም ፡ ምድረ ፡ ቢል ፤ ምድረ ፡ ከመ ፡ አድነነት ፡ ወከመ ፡ ቅሩብ ፡ ኃጒላ፡ ጥፋቷ ፡ ቅርብ፡እንደሆነና ፤ ለጥፋት ፡ እንደቀረበች ፡ ምድርን ፡ አየ ።
፪ ፤ ወአንሥአ ፡ እገሪሁ ፡ እምህየ ፡ ወሖረ ፡ እስከ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ።
ከዚያ ፡ እግሩን ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ሄደ ።
፫ ፤ ወጸርሐ ፡ ለእምኄዉ ፡ ሄኖክ ፡ ወይቤ ፡ኖኅ ፡ በቃል ፡ መሪር ፡ ስምዐኒ ፡ ስምዐኒ ፡ ስምዐኒ ፡ ሥልሰ ።
ኖኅም ፡ ሄዶ ፡ ለአያቱ ፡ ለሄኖክ፡ ጮኸ ፤ ኖኅም ፡ በሚያሳዝን ፡ ቃል ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ስማኝ ፡ ስማኝ ፡ ስማኝ ፡ አለ ፤ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ስለምን ፡ ተናገረ ፡ ቢሉ ፡ እንደ ፡ ሦስት ፡ ምስክር ፤ አንድም ፤ ስለ ፡ ሦስቱ ፡ ልጆቹ ፤ አንድም ፡ ለአጽንዖተ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ምድር ፡ ምድር ፡ ምድር ፤

ስምዒ፡ ቃለ ፡እግዚአብሔር፡ወተወከፊ ፡ ስእለተኪ[፩] ፡ እንዲል ፤

፬ ፤ ወይቤሎ ፡ ንግረኒ ፡ ምንት ፡ ውእቱ ፡ ዘይትገበር ፡ በዲበ ፡ ምድር፡

በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚሠራው ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ ንገረኝ ፡ አለው ፤

፭ ፤ እስመ ፡ ከመዝ ፡ ሰርሐት ፡ ምድር ፤

ምድር ፡ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ኃጢአት ፡ ደክማለችና ፤

ወአንቀልቀለት ፤

በኃጢአታቸው ፡ ተነዋውጣለችና፣

ዮጊ ፡ አነ ፡ እትነኩል ፡ ምስሌሃ ፤

ወይስ ፡ እኔ ፡ ከእርሷ ፡ ጋራ ፡ እጠፋ ፡ እሆን ? ወይስ ፡ ይህ ፡ ጥፋቱ፡ ይቀር ፡ ይሆን ፡ አለው፤

፮ ፤ ወበድኅረ ፡ ውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ከንሐውከ ፡ ዓቢይ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወተሰምዐ ፡ ቃል ፡ እምሰማይ ፤

ይህን ፡ ከተናገርኩ ፡ በኋላ ፡ ሁከት ፡ ሆነ ፡ መላእክት ፡ ኄኖክን ፡ ይዘው ፡ ሲመጡ ፡ በገነት ፡ ንውጽውጽታ፡ ሆነ ፤

፯ ፤ ወወደቁ ፡ በገጽየ ፤

በግምባሬ ፡ ፍግም ፡ ብዬ ፡ ወደቅሁ ፤

ወመጽአ ፡ ሄኖክ ፡ እምሔውየ ፡ ወቆመ ፡ ኀቤየ ፡ ወይቤለኒ ፡ ለምንት ጸራሕከ ፡ ኀቤየ ፡ ጽራሐ ፡ መሪረ ፡ ወብካየ ፤

እያቴ ፡ ሄኖክም ፡ ወደእኔ ፡ መጥቶ ፡ በአጠገቤ ፡ ቆመ ፤

እንዲህ ፡ ያለ ፡ የሚያሳዝን ፡ ጽኑ ፡ ልቅሶ ፡ ለምን ፡ አለቀስህ ? አለኝ ፤

፰ ፤ ወትእዛዝ ፡ ወጽአ ፡ እምኀበ፡ ገጹ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፡ ዲበ ፡ እለ ፡ የኀድሩ ፡ ውስተ ፡ የብስ፤

በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ከመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ትእዛዝ ፡ ወጥቷል ፤ ይህ ፡ መከራ ፡ ይቀራል ፡ መስሎህ ? ወይስ ፡ አንድነት ፡ እጠፋ ፡ መስሎህ ፤

ከመ ፡ ውእቱ ፡ ይኩን ፡ ኅልቀቶሙ ፤

ጥፋታቸው ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፤

፱ ፤ እስመ ፡ አእመሩ ፡ ኵሎ ፡ ኅቡዓተ ፡ መላእክት ፤

ደቂቀ ፡ ሴት ፡ የሚያውቁትን ፡ ምሥጢረ ፡ ኃጣውእን ፡ ሁሉ ፡ አውቀዋልና ፤

ወኵሎ ፡ ግፍዐ ፡ ሰይጣናት ፡

አጋንንት ፡ የሚያውቁትን ፡ ሁሉ ፡ አውቀዋልና ፤

ወኵሎ ፡ ኃይሎሙ ፡ ኅቡዐ ፡ ለእለ ፡ ይገብሩ ፡ ሥራያተ ፤

ሥር ፡ የሚምሱ ፡ ቅጠል ፡ የሚበጥሱን ፡ ሰዎች ፡ ምሥጢር ፡ አውቀዋልና ፡

ወኃይሎሙ ፡ ለኀብራት ፤

የቀለማትን ፡ ግብር ፡ አውቀዋልና ፡ በሕና ፡ መንከር ፣ በእንሶስላ፡ ማቅላት ፣ በድንጋይ ፡ ማጥቈር፤

---

፩፤ ኢሳ. ፩፥፪

ወኃይሎሙ ፡ ለእለ ፡ ይሰብኩ ፡ ሰብኮ፡ ኵሉ ፡ ምድር ፤
የዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ጣዖት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ ሥራ ፡ አውቀዋልና ፤
፲ ፤ ወእስኩ ፡ እፎ ፡ ይትወለድ ፡ ብሩር ፡ እምፀበለ ፡ ምድር ፤
እስኪ ፡ ብር ፡ ከምድር ፡ ትቢያ እንዴት ፡ ይገኝ ፡ ነበር? እንድም ፡ ብር ፡ ከትቢያ ፡ እንዲገኝ ፡ አስተምረዋልና ፡
፲፩ ፤ ወእፎ ፡ ይከውን ፡ ነጠብጣብ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤
እነሱን ፡ የሚያስገኛቸው ፡ መሬት ፡ ቀድሞ ፡ እንደተገኘ ፤ እንድም ፡ እይር ፡ ከምድር ፡ እንዲገኝ ፡ አስተምረዋልና ፤
እስመ ፡ አረር ፡ ወናዕክ ፡ ኢይትወለድ ፡ እምድር ፤
እርሳስ ፡ ቆልቆልም ፡ ከመሬት አይገኝም ፡ ነበርና ፤
ከመ ፡ ቀዳሚ ፡ ነቅዕ ፡ ውእቱ ፡ ዘይወልዶሙ ፤
እሊህን ፡ ያስገኘ ፡ መሬት ፡ ከምድር ፡ እንደተገኘ ፡ እስኪ ፡ እንዴት ፡ ይገኝ ፡ ነበር ? እንዲገኝ ፡ አስተምረዋልና ፤ እንድም ፡ እሊህን ፡ የወለደ ፡ አዳም ፡ ከምድር፡ እንደተገኘ ፡ እስኪ ፡ እንዴት ፡ ይገኝ ፡ ነበር ? ባያስተምሩ ፡ እንዲገኝ ፡ አስተምረዋልና ፤

ወመልአክ ፡ ዘይቀውም ፡ ውስቴታ ፡ ወይበድር ፡ ውእቱ ፡ መልአክ ፤
ዋዌው ፡ አይረባም ፡ በዚች ፡ ዓለም ፡ የተሾመ ፡ ዲያብሎስ ፡ ስምያዛ ፡ ኃጢአት ፡ ለመሥራት ፡ ይፋጠናል ፤
፲፪ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ አኀዘኒ ፡ እም ሑውየ ፡ ሄኖክ ፡ በእዴሁ ፡ ወአን ሥአኒ ፤
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አያቴ ፡ ሄኖክ በእጁ ፡ ይዞ ፡ አነሣኝ ፤
፲፫ ፤ ወይቤለኒ ፡ ሑር ፡ እስመ ፡ ተሰእልክዎ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ በእንተዝ ፡ ሀውክ ፡ በዲበ ፡ ምድር ፤
ስለዚህ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ስለታ ዘዘው ፡ ሁከት ፡ የመላእክትን ፡ ጌታ ፡ ጠይቄዋለሁና ፡ ሂድ ፡ አለኝ ፤
፲፬ ፤ ወይቤለኒ ፡ በእንተ ፡ ዓመፃ ሆሙ ፡ ተፈጸመት ፡ ኵነኔሆሙ ፤
ስለኃጢአታቸው ፡ ፍዳቸው ፡ ተፈ ጽሟልና ፤
ወኢይትኌለቊ፡ በቅድሜየ ፡ በእንተ አውራኅ ፡ ዘኀሠሡ ፤
ለራሳቸው ፡ ለልጆቻቸው ፡ ስለ ዘመኑ ፡ የለመኑት ፡ ልመና ፡ በፊቴ ፡ አይቈጠርላቸውምና ፤
፲፭ ፤ ወእእመሩ ፡ ከመ ፡ ምድር ፡ ትትኀጕል ፤
ምድር ፡ እንድትጠፋ ፡ እያወቁ፤
ወእለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲቤሃ ፤

በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉት ፡ እንዲ
ጠፉ ፡ እያወቁ ፤
ወለእሉ ፡ ምግባእ ፡ አልቦሙ ፡ ለዓ
ለም ፤
ለዘለዓለሙ ፡ ምላሽ ፡ የላቸው
ምና ፡ ሑር ፡ ሂድ ፡ አለኝ ፤
እስመ ፡ እርአይዎሙ ፡ ዘኀቡእ ፤
ምሥጢረ ፡ ኃጣውእን ፡ ስላሳዩ፤
ወእለ ፡ ተኰነኑ ፤
የተፈረደባቸውም ፡ ስለሆኑ ፤
ምላሽ ፡ የላቸውምና ፡ ሂድ ፡ አለኝ ፤
፲፮ ፤ ወአኮ ፡ ለከ ፡ አንተ ፡ ወልድየ ፤
ብከ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ልጄ ፤ ባንተ ፡
የሚፈረድብህ ፡ አይደለም ፤
አእመረ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡
እስመ ፡ ንጹሕ ፡ ወኄር ፡ አንተ ፤
ንጹሕ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ የመላ
እክት ፡ ጌታ ፡ አውቋልና ፤
እምዝ ፡ ኂስ ፡ ዘኀቡዓት፤
ሠውረው ፡ ከሠሩት ፡ ኃጢአት፡
ንጹሕ ፡ እንደሆንህ ፡ አውቋልና ፤
፲፯ ፤ ወአጽንዖ ፡ ለስምከ ፡ በማዕከለ ፡
ቅዱሳን ፤
በቅዱሳን ፡ መላእክት ፡ መካከል ፡
ስምህን ፡ አንተ ፡ አጽናው ፤ አን
ድም ፡ ስምህን ፡ የመላእክት ፡
ጌታ ፡ አጸናው ፤
ወየዐቅበከ ፡ እምእለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲበ
የብስ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሚኖሩ ፡ ከራ
ዓይት ፡ ይሠውርሃል ፤ አንድም፡
ከሰው ፡ ለይቶ ፡ ይጠብቅሃል ፤
ወየዐቅቡከ ፡ ቢል ፤ መላእክት ፡
ይጠብቁሃል ፤
፲፰ ፤ ወአጽንዖ ፡ ለዘርእከ ፡ በጽድቅ ፤
ልጅህን ፡ በምግባር ፡ በሃይማ
ኖት ፡ አጽናው ፤ አንድም ፡ አጽ
ንዖሙ ፡ ቢል ፡ ልጆችህን ፡ በም
ግባር ፡ በሃይማኖት ፡ አጽናቸው፤
ለነገሥት ፤
ነገሥታት ፡ ሊሆኑ ፡
ወለስብሐት ፡ ዓቢያት ፤
ካህናት ፡ ሊሆኑ ፤
ወእምዘርዕከ ፡ ይወጽእ ፡ ነቅዓ ፡ ጻድ
ቃን ፡ ወቅዱሳን ፤
ከዘርህ ፡ የደናግል ፡ የሐጋውያን
መገኛ፡ አብርሃም ፡ ይወለዳል ፤
ወኍልቍ ፡ አልቦሙ ፡ ለዓለም ፤
ለዘለዓለሙ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡
የላቸውም ፤
፲፱ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ አርአየኒ ፡ መላ
እክተ ፡ መቅሠፍት ፡ እለ ፡ ድልዋን ፡
ከመ ፡ ይምጽኡ ፡ ወይፍትሑ ፡ ኵሎ ፡
ኃይለ ፡ ማይ ፡ ዘመትሕተ ፡ ምድር ፤
ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ካየሁ ፡
በኋላ ፡ የውኃውን ፡ ቦታ ፡ ሁሉ
ይከፍቱ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚህ ፡
ዓለም ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ለመ
ዓት ፡ የተዘጋጁ ፡ መላእክተ ፡
መቅሠፍትን ፡ አሳየኝ፤

ከመ ፡ ይኩን ፡ ለዘንኔ ፡ ወለኃጕል ፡ ለዘሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ወየኀድሩ ዲበ ፡ የብስ ፧
በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለመቻያ ፡ ለጥፋት ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ምድሩን ፡በሰባ ፡ አፈው (አፎች) ፡ቀዶ ፡ አውጥቶታልና፧
፳ ፧ ወአዘዘ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስተ ፡ መላእክተ ፡ እለ ፡ ይወጽኡ ፧
ከመላእክት ፡ ጌታ ፡ ታዝዘው ፡ የሚወጡ ፡ መላእክትን ፡ አዘዘ ፧
ከመ ፡ ኢያንሥኡ ፡ እደወ ፧
ማየ ፡ አይኅን ፡ ከማምጣት ፡ እጃቸውን ፡ እንዳያነሡ ፤ ያን ሥኡ ፡ ቢል ፡ ማየ ፡ አይኅን ለማምጣት ፡ እጃቸውን ፡ ያንሱ ዘንድ ፧
ወይዕቀቡ ፧
ማየ ፡ አይኅን ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡ እስመ ፡ እልክቱ ፡ መላእክት ፡ ዲበ ፡ ኃይለ ፡ ማያት ፡ ሀለዉ ፧
እሊህ ፡ መላእክት ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ አሉና ፡ መገብተ ፡ ማያት ናቸውና ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፧
፳፩ ፧ ወወጻእኩ ፡ እምቅድመ ፡ ገጸ ፡ ሄኖክ ፧
ከሄኖክ ፡ ፊት ፡ ወጣሁ ፧
፳፪ ፧ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ኮነ ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኀቤየ ፧
ማየ ፡ አይኅን ፡ ባየሁበት ፡ ወራት ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደእኔ ፡ መጣ ፡ ከኔ ፡ ዘንድ ፡ ተነገረ ፧
፳፫ ፧ ወይቤለኒ ፡ ኖኅ ፡ ናሁ ፡ ክፍ ልከ ፡ ዐርገ ፡ ኀቤየ ፧
ኖኅ ፡ እድልህ ፡ ዕጣህ ፡ ከኔ ፡ ደረሰ ፧ ክፍል ፡ ዘአልቦ ፡ ኂስ ፧
ነውር ፡ ነቀፋ ፡ የሌለው ፡ ዕድል ፡ ዕጣ ፡ የሚሆን ፡ ኖኅ ፡ ዕድልህ ፡ ዕጣህ፧
ክፍለ ፡ ፍቅር ፡ ወርትዕ ፧
የቀና ፡ ነገርና ፡ የፍቅር ፡ ዕጣ ፡ ዕድል ፡ የሚሆን ፡ ዕጣህ ፡ ዕድ ልህ ፡ ወደእኔ ፡ ደረሰ ፧
፳፬ ፧ ወይእዜኒ ፡ ይገብሩ ፡ መላእ ክት ፡ ዕፀወ ፧
አሁንም ፡ መላእክት ፡ ዕጣ ፡ ይጥላሉ ፧
ወሶበ ፡ ወጽኡ ፡ ለውእቱ ፡ መልእክት ፧
መላእክት ፡ ዕጣ ፡ ለመጣጣል በወጡ ፡ ጊዜ ፧ አንድም ፡ ለው እቱ ፡ መልእክት ፡ ቢል ፤ ለዚህ ዕጣ ፡ ለማጣጣሉ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፧
እወዲ ፡ እዴየ ፡ ዲቤሃ ፡ ወእዐቅባ፧
እጣህን ፡ ዕጣ ፡ ሕይወት ፡ አደ ርጋታለሁ ፧ አንድም ፡ ይገብሩ ፡ ይግበሩ ፡ መላእክት ፡ ዕፀወ ፡ ሲል ፡ ነው ፧ መላእክት ፡ መር ከብ ፡ ይሥሩ ፧ ወሶበ ፡ ወጽኡ ፡ መላእክት ፤ መርከብ ፡ ሲሠሩ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፤ አንድም ፡ መል

እክት ፡ ቢል ፡ ለዚህ ፡ መርከብ ፡ ለመሥራቱ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፣ ወእወዲ ፡ እዴየ ፡ ዲቤሃ ፣ ሥል ጣኔን ፡ በእርሷ ፡ አደርጋለሁ ፤ መርከቡ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ሲቀ ረው ፡ የጐን ፡ በር ፡ አውጥቶላ ታል ፤ ማየ ፡ አይኅ ፡ እንዳይገባ ባት ፡ ሱርያል ፡ በክንፍ ፡ ጋርዷ ታልና ፡ ወአዐቅባ ፣ ማየ ፡ አይህ ፡ እንዳይገባ ፡ እጠብቃታለሁ ፤

፰፭ ፤ ወትከውን ፡ እምኔሃ ፡ ዘርአ ፡ ሕይወት ፤

መርከቧን ከመጠበቄ የተነሣ ፡ ዘርአ ፡ ሕይወት ፡ ትሆናለህ ፤ ወተውላጥ ፡ ይባእ ፡ ከመ ፡ ኢይንበር የብስ ፡ ዕራቆ ፤

ምድር፡ ዕራቍቱን ፡ እንዳይሆን በሞተው ፡ ሰው ፡ ለውጥ ፡ ውስጡ ፡ ይግባ ፤ ከሚበሉት ፡ ሰባት ፡ ሰባት ፣ ከማይበሉት ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ይዞ ፡ ገብቷልና ፤

፰፮ ፤ ወአጸንዖ ፡ ለዘርእከ ፡ በቅድ ሜየ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

በፊቴ ፡ ልጅህን ፡ በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ አጸናዋለሁ ፤ ወእዘርኦሙ ፡ ለእለ ፡ የኀድሩ ፡ ምስ ሌከ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤

ልጆችህን ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ እበትናቸዋለሁ ፡ ዘር ፡ አደርጋ ቸዋለሁ ፤

፰፯ ፤ ወይትባዛኅ ፡ ወይትባረክ ፡ ቅድመ ፡ የብስ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፤

በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ያመነ ፡ ሰውም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ይበዛል ፡ ይከብራል ፤

፰፰ ፤ ወየዐጽውዎሙ ፡ ለእልክቱ፤ መላእክት ፡ እለ ፡ አርአይዋ ፡ ለዓመፃ፤ ኃጢአትን ፣ ክህደትን ፡ ያስተ ማሩ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ አሥ ረው ፡ ያግዟቸዋል ፤

ውስተ ፡ ይእቲ ፡ ቈላ ፡ እንተ ፡ ትነድድ ፡ እንተ ፡ አርአየኒ ፡ ቀዳሚ ፡ እምሔውየ ፡ ሄኖክ ፡ በዓረብ ፡ በኀበ ፡ አድባረ፡ ወርቅ ፡ ወብሩር ፡ ወሐፂን ፡ ወነጠብጣብ ፣ ወናእክ ፤

የወርቅ ፣ የብር ፣ የብረት ፣ የእይር ፣ የቅልቅል ፡ ተራሮች ፡ ባሉበት ፡ አለ ፣ በወርቅ ፣ በብር ፡ በቅልቅል ፣ በእይር ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡ ባሉባት ፡ አያቴ ፡ ሄኖክ ፡ በምዕራብ ፡ በእኩል ፡ ባሳየኝ ፡ በም ትነድ ፡ ቦታ ፡ በገሃነም ፡ ያግዟ ቸዋል ፤

፰፱ ፤ ወርኢክዋ ፡ ለይእቲ ፡ ቈላ ፡ እንተ ፡ ሀውክ ፡ ዓቢይ ፡ ባቲ ፤ ሁከት ፡ ያለባት ፡ ገሃነምን ፡ አየሁ ፤

ወተሀውኮ ፡ ማያት ፤

ሁከተ ፡ ማያት ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ሁከተ ፡ ማያት ፡ ያለባት ፡ ገሃነ

ምን ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ ርኢ
ክዋ ፡ ለይእቲ ፡ ቈላ ፡ ወለተ
ሀውኮ ፡ ማያት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡
ተሀውኮ ፡ ማያትንም ፡ አየሁ ፤
፴ ፤ ወዝንቱ ፡ ኵሉ ፡ ሶበ ፡ ተገብረ ፡
እምውእቱ ፡ ነጠብጣበ ፡ እሳት ፤
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በተደረገ ፡ ጊዜ ፡
ከነጠብጣበ ፡ እሳቱ ፡ የተነሣ ፤
ወሀውኮሙ ፡ ዘየሀውኮሙ ፤
ከሚያውካቸው ፡ ሁከት ፡ የተ
ነሣ ፤
በውእቱ ፡ መካን ፡ ተወልደ ፡ ጼና ፡ ተይ፣
በዚህ ፡ ቦታ ፡ የድኝ ፡ ሽታ ፡
ተወለደ ፣ ትኩሱ ፡ ውሀ ፡ እንደ
ድኝ ፡ ይሸታልና ፤
ወተነብረ ፡ ምስለ ፡ እልኩ ፡ ማያት ፤
ከሰማይ ፡ የወረደው ፡ ውሀ ፡
ከምድር ፡ ካለው ፡ ውሀ ፡ ጋር
ተባበረ ፡ አንድ ፡ ሆነ ፤
፴፩ ፤ ወይእቲ ፡ ቈላ ፡ እንተ ፡ መላ
እክት ፡ እለ ፡ አስሐቱ ፡ ትነድድ ፡
መትሕተ ፡ ይእቲ ፡ ምድር ፤
ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ያሳቱ ፡ ደቂቀ ፡
ሴት ፡ የተጋዙበት ፡ ቦታ ፡ ከም
ድር ፡ በታች ፡ ትነዳለች ፤
፴፪ ፤ ወእንተ ፡ ቈላተ ፡ ዚአሃ ፡
አፍላገ ፡ እሳት ፡ ይወጽኡ ፤
በቈላነቷም ፡ የእሳት ፡ ፈሳሽ ፡
ይፈስሳል ፤ የሥጋው ፡ መከራ ፡
ከነፍስ ፡ ያደርሳልና ፤
በኀበ ፡ እለ ፡ ይትኴነኑ ፡ እልክቱ ፡
መላእክት ፡ እለ ፡ አስሐትዎሙ ፡
ለእለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤

ደቂቀ ፡ ሴት ፡ በተጋዙበት ፡ ቦታ ፡
የእሳት ፡ ፈሳሽ ፡ ይፈስሳል ፤
አንድም ፡ እነዚያ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡
በሚኰነኑበት ፡ ቦታ ፡ ወደቈላ
ዎች ፡ የእሳት ፡ ፈሳሾች ፡ ይፈ
ስሳሉ ፤
፴፫ ፤ ወይከውኑ ፡ እልክቱ ፡ ማያት ፡
በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ለነገሥት ፡
ወለአዚዛን ፡ ወለልዑላን ፡ ወለእለ ፡
የኀድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፡ ለፈውስ ፡
ነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ ወለኵነኔ ፡ መንፈስ ፤
በዚያ ፡ ወራት ፡ እሊህ ፡ ማያት
ለነገሥታቱ ፣ ለጸኑ ፣ ለኃያላኑ ፡
ለመድኃኒተ ፡ ሥጋ ፡ ለመድኃኒተ ፡
ነፍስ ፣ ለኵነኔ ፡ ሥጋ ፡ ለኩነኔ
ነፍስ ፡ ይሆናሉ ፤ አንድም ፡ ማየ ፡
አይኅ ፡ ይመጣብናል ፡ ብለው ፣
በአምልኮተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸን
ተው ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለሠሩ ፣
ለመድኃኒተ ፡ ሥጋ ፡ ለመድኃኒተ ፡
ነፍስ ፤ ማየ ፡ አይህ ፡ አይመጣ
ብንም ፡ ብለው ፡ ኃጢአት ፡ ለሚ
ሠሩ ፣ ጣዖት ፡ ለሚያመልኩ ፡
ለኵነኔ ፡ ሥጋ ፣ ለኵነኔ ፡ ነፍስ ፡
ይሆናሉ ፤ አንድም ፡ ሰብአ ፡ ትካ
ትን ፡ ያገኘ ፡ ያገኘናል ፡ ብለው ፡
በአምልኮተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸን
ተው ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለሚ
ሠሩ ፣ ለመድኃኒተ ፡ ሥጋ ፡ ለመ
ድኃኒተ ፡ ነፍስ ፤ ሰብአ ፡ ትካትን ፡
ያገኘ ፡ ያገኘናል ፡ ሳይሉ ፡ ኃጢ

አት ፡ ለሚሠሩ ፣ ጣዖት ፡ ለሚ ያመልኩ ፡ ለኮነኔ ፡ ሥጋ ፣ ለኮነኔ ፡ ነፍስ ፡ ይሆናሉ ፤ አን ድም ፡ በሥጋ ፡ መከራ ፡ ተቀብ ለዋልና ፤ ለኮነኔ ፡ ሥጋ ፡ አለ፣ የሥጋው ፡ መከራ ፡ የነፍሱን ፡ ያቀልላቸዋልና ፡ ለመድኃኒተ ፡ ነፍስ ፡ አለ ፤

፴፬ ፤ ወተውኔተ ፡ ይመልዕ ፡ መንፈ ሶሙ ፤

በነፍሳቸው ፣ በሥጋቸው ፡ መከራ ፡ መቀበል ፡ ሳለባቸው ፤ በሰውነታቸው ፡ ዋዛ ፣ ዘበሬታ ፣ ኃጢአት ፣ ጣዖት ፡ ይመላል ፤

ከመ ፡ ይትኰነኑ ፡ በሥጋሆሙ ፤

በሥጋቸው ፡ ይፈረድባቸው ፡ ዘንድ ፤

እስመ ፡ ክህድዎ ፡ ለእግዚአ ፡ መና ፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታን ፡ ክደውታልና ፤

፴፭ ፤ ወይሬእዩ ፡ ኰነኔሆሙ ፡ እንተ ፡ ኵሉ ፡ ዕለት ፤

ዘወትር ፡ የሚቀበሉትን ፡ መከራ ፡ ያያሉ ፣

ወኢየአምኑ ፡ በስሙ ፤

ስሞ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ስሙን ፡ የማ ያምኑ ፤ አንድም ፡ በስሙ ፡ የማያምኑ ፤

፴፮ ፤ ወበከመ ፡ ብዙኃ ፡ ውዕየ ፡ ሥጋሆሙ ፤

በሥጋቸው ፡ እንደተቃጠሉ ፡ መጠን ፤

ከመዝ ፡ በሙ ፡ ተውላጥ ፡ ለመንፈ ሶሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

ለዘላለሙ ፡ በነፍሳቸውም ፡ ለውጥ፡ አለ ፣ የሥጋው ፡ መከራ ፡ ከነፍስ፡ ያደርሳልና ፤

እስመ ፡ አልቦ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት፡ ዘይትናገር ፡ በነገረ ፡በክ፤

በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ዋዛ ፣ ዘበሬታ ፡ የሚናገር ፡ የለምና ፤

፴፯ ፤ እስመ ፡ ትመጽእ ፡ ኰነኔ ፡ ዲቤሆሙ ፤ እስመ ፡ የአምኑ ፡ በተው ኔተ ፡ ሥጋሆሙ ፤

በዋዛ ፡ በዘበሬታ ፡ ያምናሉና ፡ መቻያ ፡ የሚመጣባቸው ፡ ስለ ሆነ ፣

ወመንፈስ ፡ እግዚእ ፡ ይክህዱ ፤

ሕይወቱ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ይክዳሉና ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የለም ፡ ይላሉና ፤

፴፰ ፤ ወኪያሁ ፡ ማያት ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ በሙ ፡ ተውላጥ ፤

ወለእልክቱ ፡ ማያት ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ለእነዚህ ፡ ለማያት ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ መለወጥ ፡ አለባቸው ፤

እስመ ፡ ሶበ ፡ ይትኴነኑ ፡ እልክቱ ፤ መላእክት ፡ በውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ይትዌለጥ ፡ ዋዕዮሙ ፡ ለእልክቱ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ፤

እሊህ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ከተፈረ
ደባቸው ፡ በኋላ ፣ የእኒህ ፡
ውሃዎች ፡ ማቃጠል ፡ በዚያ ፡
ወራት ፡ ይለወጣልና ።
፴፱ ፤ ወሶበ ፡ የዐርጉ ፡ መላእክት ፡
ይትዌለጥ ፡ ዝኩ ፡ ማይ ፡ ዘአንቅዕት ፤
መላእክት ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡
አጥፍተው ፡ ባረጉ ፡ ጊዜ ፡ ይህ
ውሃ ፡ ይለወጣል ።
ወይቁርር ፤
ዋዕዩ ፡ ይቀዘቅዛል ፤
፵ ፤ ወሰማዕክዎ ፡ ለቅዱስ ፡ ሚካኤል፡
እንዘ ፡ ያወሥእ ፡ ወይብል ፤
ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ ሲናገር ፣
እንዲህ ፡ ሲል ፡ ሰማሁት ።
ዛቲ ፡ ኰነኔ ፡ እንተ ፡ ይትኴነኑ ፡
መላእክት ፣ ሰማዕት ፡ ይእቲ ፡ ለነገ
ሥት ፡ ወለአዚዛን ፡ ወለእለ ፡ ይእኅ
ዝዋ ፡ ለየብስ ፤
ደቂቀ ፡ ሴት ፡ የሚቀበሏት ፡ ይህች ፡
መቻያ ፡ ለነገሥታቱ ፣ ለኃያላኑ፡
ይህችን ፡ ዓለም ፡ ለሚገዟት ፣
ጽኑዓን ፡ ሁሉ ፡ የኃጢአታቸው ፡
ምስክር ፡ ናት ።
እስመ ፡ እሉ ፡ ማያተ ፡ ኰነኔ ፡
ለፈውስ ፡ ሥጋሆሙ ፡ ለመላእክት ፡
ወለሞተ ፡ ሥጋሆሙ ፤
እሊህ ፡ የመቻያ ፡ ውሀዎች ፡
ማየ ፡ አይኅ ፡ ይመጣብናል ፡
ብለው ፡ በአምልኮት ፡ ጸንተው ፣
ምግባር ፣ ትሩፋት ፡ ለሚሠሩ
ለመድኃኒተ ፡ ሥጋ ፣ ለመድ
ኃኒተ ፡ ነፍስ ፡ ይሆንላቸዋል ፣
ማየ ፡ አይኅ ፡ አያገኘንም ፡
ብለው ፡ ኃጢአት ፡ ለሚሠሩ ፣
ጣኦት ፡ ለሚያመልኩ ፡ ለሞተ
ሥጋ ፡ ለሞተ ፡ ነፍስ ፡ ይሆን
ባቸዋል ፤
፵፩ ፤ ወኢይሬእዩ ፡ ወኢየአምኑ ፡
ከመ ፡ ይትመየጡ ፡ እሙንቱ ፡ ማያት ፤
እሊህ ፡ ውሆች ፡ በሥጋ ፡ እንዳ
ስጨነቋቸው ፡ በነፍስም ፡ እንዲ
ያስጨንቋቸው ፡ አያምኑም ፡
አያውቁም ፤
ወይከውኑ ፡ እሳተ ፡ ዘይነድድ፡ለዓለም፤
ለዘለዓለም ፡ የሚነድ ፡ እሳት ፡
እንዲሆኑባቸው ፡ አያምኑም ፤
፵፪ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ወሀበኒ ፡
ትእምርተ ፡ ኵሎሙ ፡ ኅቡዓት ፡ በመ
ጽሐፍ ፡ እምሔውየ ፡ ሄኖክ ፤
ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ካየሁ ፡ በኋላ፣
የተሠወሩ ፡ የምሥጢራትን ፡
ሁሉ ፡ ምልክት ፡ አያቴ ፡ ሄኖክ፡
በመጽሐፍ ፡ ጽፎ ፡ ሰጠኝ ፤
ወምሳሊያተ ፡ ዘተውህባ ፡ ሎቱ፣
ለእርሱ ፡ የተሰጡትን ፡ ምሳሌ ፡
ነገር ፡ ጽፎ ፡ ሰጠኝ ፣
ወደመሮሙ ፡ ሊተ ፡ በነገረ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ዘምሳሌ፣
የእኔ ፡ ነገር ፡ ከተጻፈበት ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ጋራ ፡ የእርሱን ፡ ነገር ፡

አንድ ፡ አድርጎ ፡ ሰጠኝ ፤ ይህስ፡ ባለቤቱ ፡ ሄኖክ ፡ ነው ፡ ብሎ ፤ የእርሱ ፡ መጽሐፍ ፡ ከተጻፈበት መጽሐፍ ፡ የእኔን ፡ ምሳሌ ፡ አንድ ፡ አድርጎ ፡ ጽፎ ፡ ሰጠኝ፤ በዓመት ፡ ሐምስቱ ፡ ምዕት ፡ ካለው ፡ ጀምሮ ፡ ኖኅ ፡ ተናግሮ ታል ፡፡

## ምዕራፍ ፲፱

### ጉባኤ

፩ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ አውሥአ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ለሩፋኤል ፡ ኃይሉ ፡ ለመንፈስ ፡ ይመሥጠኒ ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ግብሩ ፡ ዕውቀቱ ፡ ወደኃዘን ፡ ይወስደኛል ፤

ወያምዕዐኒ ፤

ያበሳጨኛል ፡ ብሎ ፡ ለቅዱስ ፡ ሩፋኤል ፡ መለሰለት ፡ ለሰው ፡ ማዘኑ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ቢያድርበት ፡ ነውና ፤

፪ ፤ ወበእንተ ፡ ዕፀቡ ፡ ለኵነኔ ፡ እንተ ፡ ኅቡዓት ፡ ለኵነኔ ፡ መላእክት፤

ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ ልትሆን ፡ ስለ ተሰወረችው ፡ መቻያ ፡ ጭንቅ ነት ፡ ያበሳጨኛል ፤

፫ ፤ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ዘይክል ፡ ተዓግሦተ ፡ ዕፀቡ ፡ ለእንተ ፡ ተገብረት ፡ ኵነኔ ፡ ወነበረት ፤

በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ጸንታ ፡ የምት ኖር ፤ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ መቻያ፡ ልትሆን ፡ የመቻያዪነቱን ፡ ጭን ቅነት ፡ መታገሥ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ፤ ዕፀቡ ፡ ካለ ፡ ለእንተ ፡ ተገብረ ፡ ለእንተ ፡ ተገብረትም ፡ ካለ ፤ ዕፀባ ፡ ባለ ፡ በቀና ፡ ነበር ፤

ወይትመሰዉ ፡ በቅድሜሃ ፤

በዚች ፡ በመከራዪቱ ፡ ፊት ፡ እን ደሰም ፡ ይቀልጣሉ ፤

፬ ፤ ወአውሥአ ፡ ካዕበ ፡ ወይቤሎ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ለሩፋኤል ፡ መኑ ውእቱ ፡ ዘኢያረኀርኅ ፡ ልበ ፡ ዲቤሃ ፤

ዳግመኛ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ሩፋኤልን ፡ በዚህች ፡ በማየ ፡ አይኅ፡ መምጣት ፡ ልቡን ፡ የማያራራ ፡ ማነው ? ብሎ ፡ መለሰለት ፤

፭ ፤ ወኢይትሐወክ ፡ ኵልያቲሁ ፡ እምዛቲ ቃል ፤

ማየ ፡ አይኅ ፡ ትምጣ ፡ ከማለቱ የተነሣ ፡ ኵላሊቱ ፡ የማይታወክ በት ፡ ማነው ? አንድም ፡ ዘያረ ኀርኅ ፡ ወይትሐወክ ፡ መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፤ እርሱ ፡ ይጥፋ ፡ ቢል ፡ ልበናውን ፡ የሚያራራ ፤ ኵላሊቱን ፡ የሚያውክ ፡ ማነው? አንድም ፡ አውሥአ ፡ ቅዱስ ፡ ሩፋኤል ፡ ለቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ይላል ፤ መኑ ፡ ዘኢያረኀርኃ ፡ ወዘኢየሐውክ ፤ ማየ ፡ አይኅ ፡

ትምጣ ፡ ከማለቱ ፡ የተነሣ ፡ ልቡን ፡ የማያራራ ፤ ኵላሊቱን ፡ የማያውክ ፡ ማነው ? ዘኢያረኃርኅን ፡ ለቅዱስ ፡ ሚካኤል ፤ ዘያረኃርኅን ፡ ለቅዱስ ፡ ሩፋኤል ፡ ይሰጧል ፤

ኵነኔ፡ ወፅአት ፡ ዲቤሆሙ ፤

መቻያ ፡ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ላይ ፡ ወጣች ፤

እምኔሆሙ ፡ ዘአውፅእዎሙ ፡ ከመዝ፤

አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገርኩት ፡ መከራውን ፡ ከራሳቸው ፡ ያመጡት ፡ ነው ፤ መከራ ፡ ከራሱ ፡ ነውና ፡ የሚመጣ ፤

፲ ፤ ወኮነ ፡ ሶበ ፡ ቆመ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ፡ መናፍስት ፡ ከመዝ ፡ ይቤሎ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ለሩፋኤል ፤

ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት፡ ለመማለድ ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ ሩፋኤልን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፤

ወኢይከውን ፡ ሎሙ ፡ ምሕረት ፡ በውስተ ፡ ዓይነ ፡ እግዚእ ፤

በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ምሕረት ፡ አይደረግላቸውም ፤

እስመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ተምየሙ ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ተቈጥቷቸዋልና ፡ ይቅርታ ፡ አይደረግላቸውም ፡ አለ ፤

፲፩ ፤ እስመ ፡ በአምሳለ ፡ እግዚእ ፡ ይገብሩ ፡ በእንተ ፡ ዘይመጽእ ፡ ላዕሌሆሙ ፤

መቻያ ፡ የሚመጣባቸው ፡ ስለሆኑ ፡ በጌታ ፡ አምሳል ፡ ጣዖት ይሠራሉና ፤ ወኢይከውን ፡ ሎሙ፡ ላለው ፡ ይሰጧል ፤ አንድም ፡ በእንተዝ ፡ ይመጽእ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ይላል ፡ ጣዖት ፡ ስለሠሩ ፡ መቻያ ፡ ይመጣባቸዋል ፡

ኵነኔ ፡ ዘኅቡዕ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤ ለዘለዓለሙ ፡ የተሠወረ ፡ መቻያ ፡ ይመጣባቸዋል ፤

፲፪ ፤ እስመ ፡ ኢመልአክ ፡ ወኢሰብእ፡ ኢይትሜጠዉ ፡ መክፈልቶሙ ፤

መልአክም ፡ ሁኖ ፤ ሰውም ፡ ሁኖ ፤ ጻድቅም ፡ ሁኖ ፤ መቻያውን ፡ የሚቀበል ፡ የለምና ፤

አላ ፡ እሙንቱ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ ተመጠዉ ፡ ኵነኔሆሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም፤

እነሳቸው ፡ ብቻ ፡ መቻያቸውን ለዘለዓለሙ ፡ ይቀበላሉ ፡ እንጂ ፤

፲፱ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ኵነኔ ፤

የሥጋውን ፡ መከራ ፡ ከተቀበሉ በኋላ ፤

ያደነግፅዎሙ ፡ ወያምዕዕዎሙ ፤

አጋንንት ፡ በነፍስ ፡ ያስደነግጧቸዋል ፤ ያሳዝኗቸዋል ።

እስመ ፡ ዛተ ፡ ኵነኔ ፡ አርአዩ ፡ ለእለ የኀድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤

ይህችን ፡ ምሥጢረ ፡ ኃጣው እን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለሰው ሁሉ ፡ አስተምረዋልና ፤

፲ ፤ ወነዋ ፡ አስማቲሆሙ ፡ ለእል ክቱ ፡ መላእክት ፤

የደቂቀ ፡ ሴት ፡ አለቆች ፡ ስማ ቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤

ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ አስማቲሆሙ ፤

የአጋንንት ፡ አለቆች ፡ ስማቸው ይህ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ሁለት፡ አር ስት ፡ ነው ፤ ለሁለቱም ፡ ያመ ጣል ፤

፲፩ ፤ ቀዳማየ ፡ ዚአሆሙ ፡ ስምያዛ ፤ (ስማዝያ)

ለአንዱ ፡ አርእስት ፡ አመጣ ፤ የአለቃው፡ አለቃ ፡ መጀመሪያው አለቃ ፡ ስምያዛ ፡ (ስማዝያ) ፡ ነው ፤

ወካልኡ ፡ አርስጢቁፋ ፤

ሁለተኛው ፡ አርስጢቁፋ ፡ ይባ ላል ፤

ወሣልሱ ፡ አርሚን ፤

ሦስተኛውም ፡ አርሚን ፡ ነው ፡

ወራብዑ ፡ ኮከብኤል ፤

አራተኛውም ፡ ኮከብኤል ፡ ይባ ላል ፤

፲፪ ፤ ወሐምሱ ፡ ጡርኤል ፤

አምስተኛውም ፡ ጡርኤል ፡ ነው ፤

ወሳድሱ ፡ ሩምያል ፤

ስድስተኛውም ፡ ሩምያል ፡ ነው ፤

ወሳብዑ ፡ ዳንኤል ፤

ሰባተኛው ፡ ዳንኤል ፡ ይባላል ፤

ወሳምን ፡ ኑቃኤል ፤

ስምንተኛውም፡ኑቃኤል፡ ነው ፤

ወታስዕ ፡ በራቅኤል ፤

ዘጠነኛውም ፡ በራቅኤል፡ ነው፤

ወዐሥር ፡ አዛዝኤል ፤

ዐሥረኛው ፡ አዛዝኤል ፡ ነው፤

ዐሥር ፡ ወአሐዱ ፡ አርማሮስ ፤

ዐሥራ ፡ አንደኛውም ፡ አር ማሮስ ፡ ነው ፤

ዐሥር ፡ ወካልዕ ፡ በጠርያል ፤

አሥራ ፡ ሁለተኛውም ፡ በጠር ያል ፡ ነው ፤

፲፫ ፤ ዐሥር ፡ ወሣልስ ፡ በሰሳኤል፤

አሥራ ፡ ሦስተኛውም ፡ በሰሳ ኤል ፡ ነው ፤

ዐሥር ፡ ወራብዕ ፡ አናንያል ፤

አሥራ ፡ አራተኛውም ፡ አናን ኤል ፡ ይባላል ፤

ዐሥር ፡ ወሐምስ ፡ ጡርያል ፤

አሥራ ፡ አምስተኛውም ፡ ጡር ያል ፡ ይባላል ፡

ዐሥር ፡ ወሳድስ ፡ ሲማሲፒኤል ፤

አሥራ ፡ ስድስተኛውም ፡ ሲማሲ ፒኤል ፡ ይባላል ፤

፲፬ ፤ ዐሥር ፡ ወሳብዕ ፡ ይትርኤል፤

አሥራ ፡ ሰባተኛውም ፡ ይትር ኤል ፡ ይባላል ፤

ዐሥር ፡ ወሳምን ፡ ቱማኤል ፤

አሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ቱማ ኤል ፡ ነው ፤

ዐሥር ፡ ወታስዕ ፡ ጠርኤል ፤
አሥራ ፡ ዘጠነኛው ፡ ጠርኤል ፡ ነው ፤
እሥራ ፡ ሩማኤል ፤
ሃያኛውም ፡ ሩማኤል ፡ ነው ፣
እሥራ ፡ ወአሐዱ ፡ አዛዝኤል ፤
ሃያ ፡ አንደኛውም ፡ አዛዝኤል ፡ ይባላል ፤
፲፫ ፤ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ አርእስተ፡ መላእክቲሆሙ ፤
የአለቆች ፡ አለቆች ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤ አሁን ፡ የቈጠራቸው ፡ ሃያ ፡ አንዱን ፤ አንድም ፡ አሥራ ፡ ስምንቱን ፡ ተናገሮ ፡ ፫ቱን ፡ አል ተናገራቸውም ፡ ነበርና ፡ ፫ቱ ፡ አለቆች ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤
፲፬ ፤ ወአስማቲሆሙ ፡ ለመኩንን ፡ ምእተ ፡ ዚአሆሙ ፤
አንዱን ፡ አርእስት ፡ ጨርሶ ፡ አን ዱን ፡ አመጣ ፤ የመቶ ፡ አለቃ ፤
ወመኩንን ፡ ሐምሳ ፡ ዚአሆሙ ፤
የሐምሳው ፡ ደምሳሽ ፤
ወመኩንን ፡ አሥርተ ፡ ዚአሆሙ ፤
የዐሥሩ ፡ መጨኔ ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ስሙ ፡ ለቀዳማዊ ፡ ይቆን ፤
የመጀመሪያው ፡ ስሙ ፡ አዝ ማች ፡ ይቆን ፡ ይባላል ፤
፲፭ ፤ ወዝንቱ ፡ ዘአስሐተ ፡ ኵሎሙ፡ ደቂቀ ፡ መላእክት ፡ ቅዱሳን ፡ ወአው ረዶሙ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤
ቅዱሳን ፡ የነበሩ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ ፋዩድ ፡ ያወረዳቸው ፣
ወአስሐቶሙ ፡ በአዋልደ ፡ ሰብእ ፤
በአዋልደ ፡ ቃየል ፡ ያሳታቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
፲፮ ፤ ወካልእ ፡ ስሙ ፡ አስብኤል ፡ ወዝንቱ ፡ አመሮሙ ፡ ምክረ ፡ እኩየ ፡ ለደቂቀ ፡ መላእክት ፡ ቅዱሳን ፤
ሁለተኛውም ፡ ስሙ ፡ አስብኤል፡ ነው ፤ ንጹሓን ፡ ክቡራን ፡ የነበ ሩትን ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ ክፉ ፡ ምክር ፡ አመለከታቸው ፤
ወአስሐቶሙ ፡ ከመ ፡ ያማስኑ ፡ ሥጋ ሆሙ ፡ በአዋልደ ፡ ሰብእ፤
ሰውነታቸውንም፡በቃየል፡ልጆች፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አሳታቸው ፤
፲፱ ፤ ወሣልስ ፡ ስሙ ፡ ጋድርኤል ፡ ዝውእቱ ፡ ዘአርአየ ፡ ኵብጠታተ ፡ ሞት ፡ ለውሉደ ፡ ሰብእ ፤
ሦስተኛው ፡ ስሙ ፡ ጋድርኤል ፡ ነው ፤ ይህም ፡ አጋንንት ፡ ሰውን፡ መትተው ፤ ሰው ፡ ሰውን ፡ መትቶ፡ ለሞት ፡ የሚያበቃውን ፡ አመ ታት ፡ ያስተማረ ፡ ነው ፤
፳ ፤ ወውእቱ ፡ አስሐታ ፡ ለሔዋን ፣ ሔዋንንም ፡ ያሳታት ፡ እርሱ ፡ ነው ፤
ወውእቱ ፡ አርአየ ፡ ንዋየ ፡ ሞት ፡ ለደቂቀ ፡ ሰብእ፤

የሞትን መሣሪያ ፡ ያስተማረ ፤
ወልታ ፡ ወድርዓ ፤
ጥሩር ፡ መልበስን ፤ ጋሻ ፡ መስ
ጐድን ፤
ወሰይፈ ፡ ለቀትል ፤
ለሰልፍ ፡ ሾተል ፤ ጐራዴ ፤ መሥ
ራትን ፡ ያስተማረ ፤
፳፩ ፤ ወኲሎ ፡ ንዋየ ፡ ሞት ፡
ለውሉደ ፡ ሰብእ ፤
ለሰው ፡ ልጆች ፡ የሚጋደሉብ
ትን ፡ የሚዳ ፡ ፀብቱን ፡ ሁሉ ፡
ያሳየ ፤
ወእምነ ፡ እዴሁ ፡ ወፅአ ፡ ዲቤሆሙ፡
ለእለ ፡ የነድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤
በእርሱ ፡ ቃል ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ላሉ ፤
እምይእቲ ፡ ጊዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለመ
ዓለም ፤
ከዚያች ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ምጽአት ፡ ድረስ ፤ ለሚኖሡ ፡
ሰዎች ፡ ተነገረ ፤
፳፪ ፤ ወራብዕ ፡ ስሙ ፡ ፔንሙዕ ፡
ዝውእቱ ፡ ዘአርአየ ፡ ለውሉደ ፡
ሰብእ መሪረ ፤
መራራውን ፡ ብርዕ ፡ ቀርጸ ፤
ቀለም ፡ በጥብጦ ፤ ስመ ፡ አጋን
ንትን ፤ ምሥጢረ ፡ ኃጣውእ ፡
መጻፍን ፤
ወመዓርጊረ ፤
የሚጣፍጠውን ፤ ከሆነ ፡ በኋላ ፡
ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጻፍበ
ታል ፤ ትእዛዙ ፡ ይነገርበታልና ፤
አንድም ፡ መሪረ ፤ መጻፉን ፡
ወመዓርጊረ ፤ አለመጻፉን ፤ ከሆነ ፡
በኋላ ፡ ባይጻፍ ፡ ይሻል ፡ ነበረና ፤
አንድም ፡ መሪረ ፤ እንደነ ፡ አር
ዮስ ፤ እንደነ ፡ ንስጥሮስ ፡ የቀ
ለም ፡ ሠረገላ ፡ ይዞ ፡ መተርጐ
ምን ፤ ወመዓርጊረ ፡ መጻሕፍት ፡
የተናገሩትን ፡ መምህራን ፡ የተ
ረጐሙትን ፡ ይዞ ፡ መተርጐምን ፡
አሳየ ፤
፳፫ ፤ ወአርአዮሙ ፡ ኲሎ ፡ ኅቡአተ ፡
ጥበቦሙ ፤
የጥበባቸውን ፡ ምሥጢር ፡ ሁሉ ፡
አሳያቸው ፤
ወውእቱ ፡ አለበዎሙ ፡ ለሰብእ ፡
መጽሐፈ ፡ በማየ ፡ ሕመት ፤
ለሰዎችም ፡ በጥቁር ፡ ቀለም ፡
መጻፍን ፤
ወክርታስ ፤
በወረቀት ፡ መጻፍን ፡ አስተማራ
ቸው ፤ ልብ ፡ አስደረጋቸው ፤
፳፬ ፤ ወበእንተዝ ፡ ብዙኃን ፡ ይስሕቱ ፡
እምዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም፡ ወእስከ ፡
ዛቲ ፡ ዕለት ፤
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፤ እስከዚያችም ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡
ይስታሉ ፤
እስመ ፡ ኢተወልደ ፡ ሰብእ ፡
ለዘከመዝ ፤

ለእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ ሰው አልተወለደም ፣ አልተፈጠረም ፡ ነበርና ፤ ለዝ ፡ ቢል ፡ አሁን ፡ እንደተናገርሁት ፡ ሰው ፡ ለዚህ አልተወለደምና ፤

በቀለም ፡ ወበማየ ፡ ሕመት ፡ ያጽንዑ ሃይማኖቶሙ ፤

በቀይ፡ ቀለም ፣ በጥቁር፡ ቀለም፡ ጽፈው፤ ሃይማኖታቸውን፡ ያጸኑ፡ ዘንድ ፤ እንድም ፡ በቀለም ፡ በብርዕ ፡ ጽፈው ፥ ሃይማኖታቸ ውን ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፣ ጽሑፍ ፡ ኃጢአታ ፡ ለይሁዳ ፡ በቀለመ ፡ ሐዊን ፡ ወብርት[፩] ፡ እንዲል ፤ ወበማየ ፡ ሕመት ፡ ያፀንዑ ፡ ሃይማናቶሙ ፤

በጥቁር ፡ ቀለም ፡ ጽፈው ፡ ሃይ ማኖታቸውን ፡ ያጸናሉ ፣ ሰው ፡ አልተወለደምና ፤

እስመ ፡ ኢተፈጥረ ፡ ሰብእ ፡ ዘእንበለ፡ ከመ ፡ መላእክት ፡ ከመ ፡ ይንበሩ ፡ ጻድቃነ ፡ ወንጹሐነ ፤

ከመ ፡ መላእክትና ፡ ከመ ፡ ይንበሩ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ ጻድቃን ንጹሓን ፡ ሁነው ፡ እንደ ፡ መላ እክት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፣ እንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ አልተፈጠ ረም ፡ ነበርና ፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓ ለሙ ፡ እስከዚያችም ፡ ቀን ፡ ድረስ፡

ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይስታሉ ፡ አለ ፤

፳፫ ፤ ወሞት ፡ ዘኵሉ ፡ ያማስን ፡ እምኢገሠሦሙ ፡ አላ ፡ በዝ ፡ አእምሮቶሙ ፡ ይትኀጐሉ ፤

በቀይ ፡ ቀለም ፡ በጥቁር ፡ ቀለም ፡ ጽፎ ፡ ማኖርን ፡ በማወቃቸው ፡ ይጐዳሉ ፡ እንጂ ፡ እንዲህ ፡ ባያደ ርጉ ፡ ሁሉን ፡ የሚያጠፋ ፡ ሞት፡ ባልነካቸው ፡ ነበር ፤

፳፬ ፤ ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ኃይል ፡ ይበልዐኒ ፤

ጽፈው ፣ አኑረው ፣ በመጐዳታ ቸው ፣ ዕውቀት ፡ እንደ ፡ እሳት፡ በኃዘን ፡ ይበላኛል ፤

፳፭ ፤ ወሐምስ ፡ ስሙ ፡ ካዕድያዕ ፡ የአምስተኛውም ፡ ስሙ ፡ ካዕድ ያዕ ፡ ይባላል ፤

ዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ዘአርአየ ፡ ለውሉደ ሰብእ ፡ ኵሎ ፡ ዝብጠታተ ፡ እኩየ ፤

ለሰው ፡ ልጆች ፡ ክፉውን ፡ አመ ታት ፡ ያስተማረ፤

ዘነፍሳት ፤

የግዙፋኑን ፤

ወዘአጋንንት ፤

የረቂቃኑን ፡ አመታት ፡ ያሳየ፤ አንድም ፡ ዘነፍስ ፤ ሰው ፡ ሰውን ፡ መትቶ ፡ እንዲገድለው ፤ ወዘአጋ ንንት ፤ አጋንንት ፡ በሰዎች ፡ የሚ አደርጉትን ፡ ያሳየ ፡ ነው ፤

፳፮ ፤ ወዝብጠታተ ፡ ጻዕዓዕ ፡ በማ ኅፀን ፡ ከመ ፡ ይደቅ ፤

[፩] ፣ ኤር. ፲፯ ፥ ፩

ከእናቱ ፡ ማሕፀን ፡ ይወርድ ፡ ዘንድ ፡ የማኅፀኑን ፡ ፅንስ ፡ ማስ ወረድን ፡ ያሳየ ፤

ወዘብጠታተ ፡ ነፍስ ፤
ሰውን ፡ ሰው ፡ መትቶ ፡ እንዲ ገድለው ፤

፳፬ ፤ ንስከተ ፡ አርዌ ፤
እባብ ፣ ዘንዶ ፣ ሰውን ፡ ነድፎ ፡ እንዲገድለው ፤

ወንስከታተ ፡ ዘይከውን ፡ በቀትር ፤
እእምሮ ፡ ያለ ፡ በናላ ፡ ነው ፣ ፀሐይ ፡ በቀትር ፡ ማዕከለ ፡ ሰማይ ፡ ትሆናለች ፤ ፀሐይ ፡ ሲመታው ፡ አእምሮ ፡ ይበተናል፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሰውነት ፡ ይዝላል ፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ እባብ ፡ ዘንዶ ፡ ይሠለጥናልና ፤

ወልዳ ፡ ለአርዌ ፡ ዘስሙ ፡ ተባዕ ፤
ስሙ ፡ ኃያል ፣ ጽኑ ፡ የሚባል የተንከለኛ፡ ልጅ ፡ ይህን፡ ይህን፡ ሁሉ ፡ ያስተማረ ፡ ነው ፣ የአጋን ንትን ፡ ስማቸውን ፡ ስለምን ጠራ ፡ ቢሉ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ስም ፡ እንዳያወጡበት ፤ እንድም ፡ እን ዳያመልኳቸው ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፳ ፤

፩ ፤ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ኍልቊ ፡ ለከስብኤል ፡ ርእሰ ፡ መሐላ ፣
የመሐላ ፡ ፍጻሜ ፡ የሚሆን ፡ የስሙ ፡ ቁጥር ፡ ይህ ፡ ነው ።

መጥፊያውን ፡ ተናግሮ ፡ መዳኛ ውን ፡ አመጣ ፤ የመሐላ ፡ ፍጻሜ ፡ የሚሆን ፡ የከስብኤል ፡ ምሥጢሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የመሐላ ፡ ፍጻሜ ፡ አለው ፤ በእግዚአብሔር፡ ከማለ ፡ በኋላ ፡ በሌላ ፡ መማል ፡ አይገባምና ፣
ክስብኤል ፡ ማለት ፡ አምላክ ፡ ወሰብእ ፡ ማለት ፡ ነው ፤

ዘአርአየ ፡ ለቅዱሳን ፡ ሶበ ፡ የኀድር ልዑል ፡ በስብሐት ፣
እግዚአብሔር ፡ በማሕፀነ ፡ ማር ያም ፡ በክብር ፡ ባደረ ፡ ጊዜ ፡ ለቅዱሳን፡ ያሳየው፤(የገለጠው)፤

፪ ፤ ወስሙ ፡ ቤቃ ፣
ስሙ ፡ ቤቃ ፡ ነው ፤ ይኸውም፡ በቀዳሚ ፡ ሀለወ ፡ ቃል ፤ ቀዳ ሚሁ ፡ ቃል ፡ ማለት ፡ ነው ፤

ወዝንቱ ፡ ይቤሎ ፡ ለቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ያርእዮሙ ፡ ስሞ ፡ ኅቡዐ ፡ ከመ፡ ይርእ ይዎ ፡ ለውኡቱ ፡ ስም ፡ ኅቡዕ ፣
ይኸውም ፡ አጋንንት ፡ ያንን ፡ የተ ሠወረ ፡ ስሙን ፡ ይሰሙት ፡ ዘንድ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ የተሠወረ፡ ስሙን ፡ ግለጥላቸው ፡ አለው ፤

፫ ፤ ወከመ ፡ ይዝክርዎ ፡ በመሐላ ፡ ከመ ፡ ይርዓዱ ፡ እምውእቱ ፡ ስም ፡ ወመሐላ ፡ እለ ፡ አርአዩ ፡ ለውሉደ ፡ ሰብእ ፡ ኵሎ ፡ ዘኅቡዕ ፤
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ምሥጢረ ፡ ኃጣውእን ፡ ያሳዩ ፣ ደቂቀ ፡ ሴት ፣

አጋንንት ፡ ከዚህ ፡ ስም ፡ የተነሣ፡ ይርዱ ይንቀጠቀጡ ፡ ዘንድ ፤ በመሐላም ጊዜ ፡ ይጠሩት ፡ ዘንድ ፡ ያንን የተሠወረ ፡ ስሙን ፡ ግለጥላቸው ፡ አለው ፤

፩ ፤ ወዝንቱ ፡ ኃይሉ ፡ ለዝ ፡ መሐላ፤ የዚህ ፡ ስም ፡ ምሥጢር ፡ ይህ ነው ፤

እስመ ፡ ኃያል ፡ ውእቱ ፡ ወጽኑዕ ፤ ኃይለኛ ፡ ነውና ፡ የጸናም ፡ ነውና ፤

፩ ፤ ወአንበሮ ፡ ለዝኩ ፡ መሐላ፤ አካዕ ፡ በእዴሁ ፡ ለቅዱስ ፡ ሚካኤል ፤

ይህን፡ ስም ፡ አካዕ ፡ በቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ እጅ ፡ ጻፈው ፤ ስመ መሐላ ፡ ዘጸበጠ[፩] ፡ እንዲል ፤ አንድም ፡ በቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ቃል እንዲነገር ፡ አደረገው ፤ አካዕ ፡ ማለት ፡ አምላክ ፡ ከሃሊ ማለት ፡ ነው ፤

ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ ኅቡዓቲሁ ፡ ለዝ መሐላ ፤

የዚህም ፡ ስም ፡ የተሰወሩ ፡ ምሥጢሮቹ ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤

ወጽንዑ ፡ በመሐላሁ ፤

ፍጥረታቱም ፡ ሁሉ ፡ በመሐላው ፡ ጸኑ ፤

፮ ፤ ወሰማይ ፡ ተሰቅለ ፤

ሰማይ ፡ በዚህ ፡ ቃል፡ ጸና ፤

፩፦ ደራሲ

ዘእንበለ ፡ ይትፈጠር ፤ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤

ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ ዓለም ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር፡ ቃል ፡ ሰማይ ፡ ተፈጠረ ፤

ወቦቱ ፡ ምድር ፡ ተሣረረት ፡ ዲበ ፡ ማይ፤

ምድርም ፡ በእርሱ ፡ በውሃው ፡ ላይ ፡ ተፈጠረች ፤

፯ ፤ ወእምነ ፡ ኅቡዓተ ፡ አድባር ፡ ይመጽኡ ፡ ላህያት ፡ ማያት ፡ እምፍጥረተ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤

ጽሩያን ፡ ማያት ፡ ሲል ፡ነው ፤ ከኅቡዓን ፡ አድባር ፡ ከተራሮችም ፡ ውስጥ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ የጣፈጡ ፡ ውሃዎች ፡ ጽሩያን ፡ ማያት ፡ ይፈስሳሉ ፤ አንድም ፡ ለሕያዋን ፡ ቢል ፡ በነፍስ፡ በደመ ፡ ነፍስ ፡ ሕያዋን ፡ ለሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ይፈስሳሉ ፤

፰ ፤ ወበውእቱ ፡ መሐላ ፡ ተፈጥረት ፡ ባሕር ፤

በዚህም ፡ ስም ፡ ባሕር ፡ ተፈጠረች ፤

ወመሠረታ ፤

ከታች ፡ ነፋስ ፤ ቀጥሎ ፡ እሳት ፤ ቀጥሎ ፡ ውሃ ፤ በዚያ ፡ ላይ ፡ መሬት ፡ አድርጎ ፡ በዚህ ፡ ቃል ተፈጠረች ፤

ለጊዜ ፡ መዓት ፡ እንበረ ፡ ላቲ ፡ ኖኅ፡ ወኢተሐልፍ ፡ እምፍጥረተ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤
በተቈጣችም ፡ ጊዜ ፡ ዓለም ፡ ከተ ፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ከወሰኗ ፡ እንዳታልፍ ፡ አሽዋ ፡ አኖረላት ፣ በአሸዋ ፡ ገደ ባት ፤
፱ ፤ ወበውእቱ ፡ መሐላ ፡ ቀላያት ፡ ጸንዑ ፡ ወቆሙ ፤
በዚህም ፡ ስም ፡ ጥልቅ ፡ ውሀ ዎች ፡ ሁሉ ፡ ጸንተው ፡ ኖሩ ፣ (መሐላ ፡ የሚለውን ፡ ስም ፡ እያልህ ፡ ተርጒም ፡)
ወኢይትሐወሱ ፡ እመካኖሙ ፡ እም ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓ ለሙ ፡ ድረስ ፡ ከቦታቸው ፡ አይ ወጡም ፤
፲ ፤ ወበውእቱ ፡ መሐላ ፡ ፀሐይ ፡ ወወርኅ ፡ ይፌጽሙ ፡ ምሕዋሮሙ ፤
በዚያም ፡ ስም ፡ ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፡ አካሄዳቸውን ፡ ይፈጽማሉ ፤
ወኢየኀልፉ ፡ እምትእዛዞሙ ፡ እም ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለ ዓለሙ ፡ ድረስ ፡ ካዘዛቸው ፡ ትእ ዛዝ ፡ አልወጡም ፤ ከሰው ፡ በቀር ፡ ከትእዛዙ ፡ የወጣ ፡ የለም ፡ ለማ ለት ፣ በዚያ ፡ ስም ፡ ኮከቦች ፡ ጕዳናቸውን ፡ ይጨርሳሉ ፤ ስማ ቸውንም ፡ ይጠራል ፤

፲፩ ፤ ወበውእቱ ፡ መሐላ ፡ ከዋክብት ፡ ይፌጽሙ ፡ ምሕዋሮሙ ፡ ወአስማቲ ሆሙ ፡ ይጼውእ ፣
በዚያም ፡ ስም ፡ ኮከቦች ፡ ጕዳ ናቸውን ፡ ይጨርሳሉ ፤ ስማቸ ውንም ፡ ይጠራል ፤ ያዝዛቸዋል ፤
ወያወሥእዎ ፡ እምዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓ ለሙ ፡ ድረስ ፡ ይታዘዙለታል ፤
፲፪ ፤ ወከመዝ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ለማ ያት ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ነፋሳት ፤
ወከመዝ ፡ ማያት ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ነፋሳት ፡ ሕይወታቸው ፡ የሚ ሆኑ ፡ ማያት ፡ ተፈጥሮዋቸው እንዲህ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ወከ መዝ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ለማያት ፡ ነፋሳት ፡ ይላል ፣ ነፋሳት ፡ ሕይወ ታቸው ፡ የሚሆኑ ፡ የማያት ፡ አካላቸው ፡ እንዲህ ፡ ነው ፤ አን ድም ፡ ወከመዝ ፡ ነፋሳት ፡ ነፍ ሳቲሆሙ ፡ ለማያት ፡ ይላል ፣ የማያት ፡ ሕይወታቸው ፡ የሚ ሆኑ ፡ ነፋሳት ፡ እንደዚህ ፡ ነው፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ተፈጠሩ ፤
ወለኵሎሙ ፡ መናፍስቲሆሙ ፡ ወፍናዋቲሆሙ ፣
የፍጥረታት ፡ ሕይወት ፡ የሚ ሆኑ ፡ ነፋሳት ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ተፈጠሩ ፤

ወእምኵሉ ፡ ኀብራተ ፡ መናፍስት ፤
ከነፋሳት ፡ ቅመምነት ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ ሥርዓታቸው ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ተፈጠሩ ፤ ቅመምነት ፡ አለ፤ አራት ፡ ነፋሳተ ፡ ምሕረት ፤ ስም ንት ፡ ነፋሳተ ፡ መዓት ፡ አሉና፤
፲፫ ፤ ወበህየ ፡ ይትዐቀቡ ፡ መዛግብተ ፡ ቃሉ ፡ ለነጐድጓድ ፡ ወብርሃኑ ፡ ለመ ብረቅ ፤
የመብረቅ ፡ ብርሃኑ ፡ የሚታይባ ቸው ፡ የነጐድጓድ ፡ ድምጹ ፡ የሚ ሰማባቸው ፡ ቦታዎች ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ይጠበቃሉ ፤
፲፬ ፤ ወበህየ ፡ ይትዐቀቡ ፡ መዛግብተ ፡ በረድ ፡ ወአስሐትያ ፡ ወመዛግብተ ፡ ጊሜ ፡ ወመዛግብተ ፡ ዝናም ፡ ወጠል፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የጊሜ ፤ የው ርጭ ፤ የበረድ ፤ ቦታዎች ፤ የጉም ፡ ቦታዎች ፤ የዝናምና ፡ የጤዛ ፡ ቦታዎች ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ይጠበቃሉ ፤
፲፭ ፤ ወኵሎሙ ፡ እሙንቱ ፡ የአ ምኑ ፡ ወየአኵቱ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ወይሴብሑ ፡ በኵሉ ፡ ኃይሎሙ ፤
እነዚያ ፡ ሁሉ ፡ እምላክነቱን ፡ አምነው ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ያመሰግናሉ ፤ በፍጹም ኃይላቸው ፡ ያመሰግናሉ ።
፲፮ ፤ ወሲሳዮሙ ፡ በኵሉ ፡ አኰቴት ፡ ይእቲ ፤
በጊዜያቱ ፡ ሁሉ ፡ ምግባቸው ፡ ምስጋና ፡ ናት ፤
ወየአኵቱ ፡ ወይሴብሑ ፡ ወያሌዕሉ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ ፤ ለዘለ ዓለሙ ፡ የሚኖር ፡ የነፍሳት ጌታን ፡ ስሙንም ፡ ያከብራሉ ፤
፲፯ ፤ ወዲቤሆሙ ፡ ጸንዐ ፡ ዝ ፡ መሐላ ፤
ይህም ፡ ስም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ጸና ፤
ወይትዐቀቡ ፡ ቦቱ ፤
በእርሱም ፡ ይጠበቃሉ ፤
ወፍናዋቲሆሙ ፡ ይትዐቀቡ ፤
ሥራዎቻቸውም ፡ ይጠበቃሉ ፤
ወምሕዋራቲሆሙ ፡ ኢይማስን ፤
ጐዳናቸውም ፡ አይጠፋም ፤
፲፰ ፤ ወኮነሙ ፡ ፍሥሐ ፡ ዓቢየ ፤
ይኸውም ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሆነላ ቸው ፤
ወባረኩ ፤ ወሰብሑ ፤ ወአልዐሉ ፡ በእንተ ፡ ዘተከሥተ ፡ሎሙ ፡ ስሙ ፡ ለወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፤
ከአዳም ፡ የተወለደ ፡ የክርስቶስ ስሙ ፡ ስለ ፡ ተገለጠላቸው ፡ እርሱን ፡ አከበሩ ፤ ፈጽመውም፡ አመሰገኑ ፤
፲፱ ፤ ወነበረ ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤
በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ላይም ፡ ተቀ መጠ ፤

ወርእሱስ ፡ ለኵነኔ ፡ ተውህበ ፡ ሎቱ ለወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፤
ለአዳም ፡ ልጅ ፡ ለክርስቶስም ፡ የፍርድ ፡ ፍጻሜ ፡ ተሰጠው፤
የፍርድ ፡ ፍጻሜ ፡ ንው ፡ ኅቤየ፡ ሑሩ ፡ እምኔየ ፡ ማለት ፡ ነው፤
፳ ፤ ወያኀልፍ ፡ ወያማስን ፡ ኃጥአነ፡ እምገጸ ፡ ለምድር ፤
ከመንግሥተ ፡ ስማያትም ፡ ቦታ ኃጥአንን ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠፋል ፤
ወእለ ፡ አስሐትዎ ፡ ለዓለም ፡ በሰና ስል ፡ ይትአሠሩ ፤
ሰውን ፡ ያሳቱ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትም በሰንሰለት ፡ ይታሠራሉ ፡ አለ ፤ በፍዳ ፡ ይያዛሉ ፤
፳፩ ፤ ወበማኅበሮሙ ፡ ዘሙስና ፡ ይትዐጸዉ፤
ጥፋት ፡ ሞት ፡ ባለበት ፡ ቤታ ቸው ፡ ይጋዛሉ ፤ አንድም ፡ ማኅ በሮሙ ፡ ቢል ፡ ጥፋት ፡ ሞት ፡ ወደሚስማማቸው ፡ ወገኖቻቸው ፡ ይጋዛሉ ፤
ወኵሉ ፡ ምግባሮሙ ፡ የኀልፍ ፡ እም ቅድመ ፡ ገጸ ፡ ለምድር ፤
ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ያልፋል ፤ ይጠፋል ፤
፳፪ ፤ ወእምይእዜሰ ፡ ኢይከውን ፡ ዘይማስን ፤
ከዚያም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ከጻድ ቃን ፡ የሚጠፋ ፡ የለም ፤ ይከ ውን ፡ ቢል ፡ የኃጥአን ፡ ወገን ፡ የሚጠፉ ፡ ይሆናሉ ፤

እስመ ፡ ውእቱ ፡ ወልደ ፡ ብእሲ ፡ ተርእየ ፡ ወነበረ ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤
ብእሲ ፡ ያለው ፡ አዳምን ፡ ነው ፤ ከአዳም ፡ የተወለደ ፡ ክርስቶስ ፡ ታይቷልና፤ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጧልና ፤
ወኵሉ ፡ እኩይ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ የኀልፍ ፤
ኃጢአት ፡ ክህደት ፡ ኃጥእ ፡ መናፍቅ ፡ ከፊቱ ፡ ይጠፋል ፤
፳፫ ፤ የሐውሩ ፡ ወይነግሩ ፡ ለውእቱ፡ ወልደ ፡ ብእሲ ፡ ወይጸንዕ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ሄደውም ፡ ከአዳም ፡ ለተወለደ፡ ክርስቶስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳሉ ኃጢአታቸውን ፡ ይናገራሉ ፤ ማረኝ ፡ ማረኝ ፡ ይላሉ ፤ በነፍ ሳት ፡ ጌታ ፡ ፊትም ፡ ፍርዱ ፡ ይጸናል ፤
ወዝውእቱ ፡ ሣልስ ፡ ምሳሌ ፡ ዘሄ ኖክ ፤
የሄኖክ ፡ ሦስተኛ ፡ ነገሩ ፡ ይህ ነው ፤
፳፬ ፤ ወኮነ ፡ እምድኅረዝ ፡ ተለዐለ ፡ ስሙ ፡ ሕያው ፡ በኀቤሁ ፡ ለውእቱ ፡ ወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው፡ በኀበ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡
በኀቤሁና ፡ በኀበ ፡ እግዚአ ፡ መና ፍስት ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ በእግዚአ ፡ ነፍሳት ፡ ዘንድ ፡

የወልድ ፡ ሕያው ፡ ስሙ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ፤
እምአለ ፡ የነድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ካሉ ፡ ሰዎች ፡ ተለይቶ ፤
፳፭ ፤ ወተለዐለ ፡ በሠረገላተ ፡ መንፈስ ፤
በሀብተ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ከበረ ፡ ማለት ፡ ሀብታተ ፡ መን ፈስ ፡ ቅዱስን ፡ በመስጠት ፡ የባሕርይ ፡ ጌትነቱን ፡ ገለጸ ፤
አንድም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ባደረባቸው ፡ በሐዋርያት ፡ ቃል ክርስቶስ ፡ ተሰበከ ፤
ወወፅአ ፡ ስም ፡ በማዕከሎሙ ፤
በሐዋርያት ፡ በምእመናን ፡ መካ ከል ፡ ይህ ፡ ስም ፡ ተነገረ ፡ አለ፤
ቀዳማዊ ፡ አምላክ ፡ ተባለ ፤
፳፮ ፤ ወእምይእቲ ፡ ዕለት ፡ ኢተ ስሕብኩ ፡ በማዕከሎሙ ፤
አራቱን ፡ መዓዝን ፡ ዙሬ ፡ ካየሁበት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በመላ እክት ፡ መካከል ፡ አልሄድኩም፤
፳፯ ፤ ወአንበሩኒ ፡ በማዕከለ ፡ ፪ቱ ፡ መናፍስት ፤
በሁለቱ ፡ መዓዝን ፡ መካከል ፡ አስቀመጡኝ ፤
በማዕከለ ፡ መስዕ ፡ ወዓረብ ፤
መዓዝን ፡ ያለውን ፡ አመጣ ፡ በምዕራብና ፡ በሰሜን ፡ መካከል አኖሩኝ ፤
በኀበ ፡ ነሥኡ ፡ አሕባላተ ፡ መላእክት ከመ ፡ ይስፍሩ ፡ ሊተ ፡ መካነ ፡ ለኅሩያን ፡ ወለጻድቃን ፤
ለደናግል ፡ ለሕጋውያን ፡ ቦታ ፡ ይሰፍሩ ፡ ዘንድ ፤ መላእክት ፡ ገመዶችን ፡ በያዙበት ፡ ቦታ ፡ የደናግልን ፡ የሕጋውያንን ፡ ቦታ ያሳዩኝ ፡ ዘንድ ፡ ዕውቀትን ፡ ሥልጣንን ፡ ገንዘብ ፡ ባደረጉበት ቦታ ፡ አስቀመጡኝ ፤
፳፰ ፤ ወበሀየ ፡ ርኢኩ ፡ አበው ቀደምተ ፡ ወጻድቃነ ፡ እለ ፡ እም ዓለም ፡ በውእቱ ፡ መካን ፡ የነድሩ ፤
ከዚያም ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የነ በሩ ፡ አበው ፡ ጻንተው ፡ የነበሩበ ትን ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤
፳፱ ፤ ወከነ ፡ እምድኅረዝ ፡ ከመ ፡ ትትከበት ፡ መንፈስየ ፤
መካነ ፡ ጻድቃንን ፡ ካየሁ ፡ በኋላ፤ ልቡናዬ ፡ ትራቀቅ ፡ ጀመረች ፤
ወትዕርግ ፡ ውስተ ፡ ሰማየ ፡ ሰማያት ፤
ከሰማዮች ፡ በላይ ፡ ወዳለች ፡ ወደ ፡ ጽርሐ ፡ አርያምም ፡ ትወጣ ፡ ጀመረች፤
፴ ፤ ርኢክዎሙ ፡ ለውሉዶሙ ፡ ለመላእክት ፡ ቅዱሳን ፡ ይከይዱ ፡ ዲበ ፡ ላህበ ፡ እሳት ፤
የመላእክት ፡ ልጆች ፡ ጻድቃንን በእሳት ፡ ላይ ፡ ቁመው ፡ አየሁ አለ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ከብረው ፤
ወአልባሲሆሙ ፡ ጸዓዳ ፤
ልብሳቸው ፡ ንጹሕ ፡ ነው፤
ወአጽፎሙኒ ፤

መጉናጸፊያቸው ፤
ወብርሃነ ፡ ገጾሙ ፡ ከመ ፡ በረድ ፤
የፊታቸው ፡ ብርሃን ፡ እንደ ፡ በረድ ፡ ነው ፤ ጸጋቸው ፡ ክብራቸው ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፤
፴፩ ፤ ወርኢኩ ፡ ፪ተ ፡ አፍላጋተ ፡ እሳት ፤
በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የሚተረጉሙ ፡ ብሉያትን ፡ ሐዲሳትን፡ አየሁ ፤
ወብርሃነ ፡ ዝኩ ፡ እሳት ፡ ከመ ፡ ያክንት ፡ ያበርህ ፤
ዘርፋን ፡ ባለቤት ፡ አድርጎ ፡ አመጣው ፤ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ዕውቀቱ ፡ ያክንት ፡ እንደሚባል ፡ ዕንቍ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ ምሳሌ ፡ ቢያጣለት ፡ ነው ፤
ወወደቁ ፡ በገጽየ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ መናፍስት ፤
በሀብታት ፡ ጌታ ፡ ፊትም ፡ በፊቴ፡ ፍግም ፡ ብዬ ፡ ወደቅሁ ፤
፴፪ ፤ ወሚካኤል ፡ መልአክ ፡ ፩ዱ፡ እምእርእስተ ፡ መላእክት ፡ አኀዘኒ ፡ እዴየ ፡ ዘየማን ፡ ወአንሥአኒ ፤
ከመላእክት ፡ አለቆች ፡ አንዱ፡ መልአክ ፡ ሚካኤል ፡ ቀኝ ፡ እጄን ፡ ይዞ ፡ አስነሣኝ ፤
ወአውጽአኒ ፡ ኀበ ፡ ኵሉ ፡ ኀቡዓተ ፡ ምሕረት ፤
የምሕረቱን ፡ ምሥጢር ፤
ጠኀቡዓተ ፡ ጽድቅ ፤
የጽድቅ ፡ ምሥጢር ፡ ወደ ፡ ተሠወረበት ፡ ቦታ ፡ አወጣኝ ፤
፴፫ ፤ ወአርአየኒ ፡ ኵሉ ፡ ኀቡዓተ ፡ አጽናፈ ፡ ሰማይ ፤
በጽንፈ ፡ ሰማይ ፡ ያለውን ፡ የሚደረገውን ፡ ምሥጢር ፤
ወኵሉ ፡ መዛግብተ ፡ ከዋክብት ፡ ወብርሃናት ፡ ኵሉሙ ፡ እምኀበ ፡ ይወፅኡ ፤
የከዋክብትንም ፡ ቦታዎች ፡ ሁሉ ፡ ለሰው ፡ ሊያበሩ ፡ የሚወጡበትን፡ ቦታዎች ፡ አሳየኝ ፤
ለገጸ ፡ ቅዱሳን ፤
በጻድቃን ፡ ፊት ፡ ፀሐይ ፡ ጨረቃ ፡ የሚወጡበትን ፡ የሚገቡበትን ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤
፴፬ ፤ ወከበቶ ፡ መንፈስ ፡ ለሄኖክ፡ ውስተ ፡ ሰማየ ፡ ሰማያት ፤
ወከበተኒ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ሄኖክን ፡ ከሰማየ ፡ ሰማያት ፡ በላይ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሠወረኝ ፤
፴፭ ፤ ወርኢኩ ፡ በሀየ ፡ ማዕከለ ዝኩ ፡ ብርሃን ፡ ከመ ፡ ቦቱ ፡ ዘይት ነደቅ ፡ እምዕብነ ፡ አስሐትያ ፤
በዚያም ፡ ብርሃን ፡ መካከል ፡ አስሐትያ ፡ ከሚባል ፡ ዕንቍ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የከበረ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን፡ አየሁ ፤
፴፮ ፤ ወማዕከለ ፡ እሙንቱ ፡ አዕባን፡ ልሳናተ ፡ እሳት ፡ ዘሕያው ፤

በእሊህ : አዕናቍ : መካከል : የሕያው : እሳት : አንደበቶች : አሉ ፤ አንድም : በመንግሥተ : ሰማያት : መካከል : በመንፈስ ቅዱስ : ተገልጾላቸው : ብሉያ ትን : ሐዲሳትን : አስተምረው : ከግብር : ገብተው : ሥራ : የሠሩ : ሰዎች : አሉ ፤

፮ ፤ ወርእየት : መንፈስየ : ዓውደ : ዘየዓውዶ : ለውእቱ : ቤት : እሳት : እምአርባዕቱ : አጽናፊሁ : ለውእቱ፡ አፍላጋት : ምሉዓነ : እሳት : ሕያው፤

እሳት : የሚከበውን : ቤት ፣ በአራቱ : ማዕዘን : አፍላጋት : የከበቡትን ፣ እሳት : የሚከበ ውን : ቤት : አየሁ ፤ አንድም : እሳት : የመላበትን : አፍላጋት : በአራቱ : ማዕዘን : የከበቡትን : ቤቱን ፣ የከበበውን : እሳቱን : አየሁ ፤ አንድም : በመንፈስ : ቅዱስ : ተገልጾላቸው : ብሉያት : ሐዲሳትን : አስተምረው : ከግ ብር፡ ገብተው : ሥራ : የሠሩ : ጻድቃን ያሉባት : መንግሥተ : ሰማያትን : አየሁ፤

፯ ፤ ወየዓውድዎ : ለውእቱ : ቤት : በአውዱ : ኪሩቤል : ወሱራፌል : ወአፍኒን : እሉ : እሙንቱ : እለ : ኢይነውሙ ፤

ኪሩቤልና : ሱራፌል : አፍኒንም : የዚህን : ቤት : ዙሪያውን : ከበ ውታል ፣ እነዚህም : የማያርፉ : ናቸው ፣

ወየዓቅቡ : መንበረ : ስብሐቲሁ ፤

የጌትነቱን : ዙፋን : ይጠብቃሉ፤ ጠላት : ኑሮበት : ማለት : አይ ደለም ፣ ደጅ : የሚጠኑት : የሚ ከቡት : ሲል : ነው ፤

፰ ፤ ወርኢኩ : መላእክተ : እለ ኢይትኌለቁ : አእላፈ : አእላፋት : ወትእልፌተ : አእላፈት ፤

የማይቈጠሩ : የብዙ : ብዙ : የሚ ሆኑ : መላእክትን : አየሁ ፤

ወየዐውድዎ : ለውእቱ : ቤት ፤

ያንንም : ቤት ፣ ይከቡታል ፤

፱ ፤ ሚካኤል : ወገብርኤል ፣ ሩፋኤል : ወፋኑኤል፣መላእክት : ቅዱሳን : እለ : መልዕልተ : ሰማያት : ይበውኡ ፤ ወይወጽኡ : በውእቱ : ቤት ፣

በሰማያት : ያሉ : ቅዱሳን : መላ እክት : ሚካኤልና : ገብርኤል ፣ ሩፋኤልና : ፋኑኤል ፣ በዚያ : ቤት : ይገባሉ ፣ ይወጣሉ ፤ በቤተ : መንግሥት : አምሳል : ለተልዕኮ፤ አንድም : ሰው : የጸለየውን : ጸሎት ፣ የሠዋውን : መስዋዕት: ለማሣረግ : የመውጣታቸው : የመውረዳቸው : አምሳል ፤

፲ ፤ ወወጽኡ : እምውእቱ : ቤት : ሚካኤል : ወገብርኤል ፣ ሩፋኤል : ወፋኑኤል ፣ ወብዙኃን : ቅዱሳን ; መላእክት : እለ : አልቦሙ : ኍልቈ ፤

ከዚያም ፡ ቤት ፡ ሚካኤልና ፡ ገብርኤል ፤ ሩፋኤልና ፡ ፋኑኤ ልም ፤ ብዙ ፡ የሆኑ ፤ ቁጥር ፤ የሌላቸው ፡ ሌሎች ፡ የከበሩ ፡ መላእክትም ፡ ወጡ ፤

፵፪ ፤ ወምስሌሆሙ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፤
ብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ጌታ ፡ ከእነ ርሱ ፡ ጋራ ፡ አለ ።

ወርእሱ ፡ ከመ ፡ ፀምር ፡ ጸዓዳ ፤
ራሱም ፡ እንደ ፡ ብዝት ፡ ነጭ ነው ፤

ወንጹሕ ፤
ንጹሐ ፡ ባሕርይ ፡ ነው ፤

ወልብሱ ፡ ዘኢይተረጎም ፤
ባሕርዩ ፡ የማይመረመር ፡ ነው ፤

፵፫ ፤ ወወደቁ ፡ በገጽየ ፡ ወኵሉ ፡ ሥጋየ ፡ ተመስወ ፤
እኔም ፡ በግምባሬ ፡ ፍግም ፡ ብዬ ፡ ወደቅሁ ፤ ሥጋዬም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ቀለጠ ፤

ወመንፈስየ ፡ ተወለጠ ፤
አዕምሮዬም ፡ ተለወጠ ፤

፵፬ ፤ ወጸራኅኩ ፡ በቃል ፡ ዓቢይ ፡ በመንፈስ ፡ ኃይል ፤
ዕውቀትን ፡ በያዘ ፡ ልቡና ፤ ዕው ቀትን ፡ በሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አሰምቼ ፡ ተናገርኩ ፡

ወባረኩ ፡ ወሰባሕኩ ፡ ወአልዐልኩ ፤
ፈጽሜም ፡ እርሱን ፡ አመሰገንሁ ስሙንም ፡ አከበርኩ ፤

፵፭ ፤ ወእላ ፡ በረከታት ፡ እለ ፡ ወፅአ ፡ እምነ ፡ አፉየ ፡ ኮና ፡ ሥሙ ራተ ፡ በቅድመ ፡ ዝኩ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፤
ከአፌ ፡ የወጡ ፡ እሊህ ፡ ምስጋ ናዎች ፤ ጸሎታት ፡ የተወደዱ ፡ ሆኑ ፤

፵፮ ፤ ወመጽአ ፡ ውእቱ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፡ ምስለ ፡ ሚካኤል ፡ ወገ ብርኤል ፤ ሩፋኤል ፡ ወፋኑኤል ፤ ወአእላፍ ፡ ወትእልፊተ ፡ አእላፋት ፡ መላእክት ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ኍልቍ ፤
ጌታ ፡ ሚካኤልና ፡ ገብርኤልን ፤ ሩፋኤልና ፡ ፋኑኤልን ፤ ሌሎች የብዙ ፡ ብዙ ፡ የሚሆኑ ፡ መላ እክትን ፡ አስከትሎ ፡ መጣ ፤

፵፯ ፤ ወመጽአ ፡ ኀቤየ ፡ ውእቱ ፡ መልአክ ፡ ወበቃሉ ፡ አምኃኒ ፤
ተናገረኒ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ያም ፡ መልአክ ፡ ወደእኔ ፡ መጣ ፤ በቃ ሉም ፡ ተናገረኝ ፤

፵፰ ፤ ወይቤለኒ ፡ አንተ ፡ ውእቱ ፡ ወልደ ፡ ብእሲ ፡ ዘተወለድከ ፡ ለጽድቅ ፤
ለበጎ ፡ ሥራ ፡ የተወለድህ ፡ የባለ አእምሮ ፡ ልጅ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤

ወጽድቅ ፡ ላዕሌከ ፡ ኀደረ ፤
ረድኤት ፡ ክብር ፡ በላይህ ፡ ላይ ፡ አደረ ፤

ወጽድቁ ፡ ለርእሰ ፡ መዋዕል ፡ ኢየኀድገከ ፤
የብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ክብሩ ፡ አይለይህም ፤ ረድኤቱ ፡ አይር ቅህም ፤

፲፬ ፧ ወይቤለኒ ፡ ይጼውዕ ፡ ለከ ሰላመ ፡ በስሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ ዘይከውን ፧
በስሙ ፡ ላመኑ ፡ ለጻድቃን ፡ የሚ ሰጠው ፡ ክብር ፡ ይሰጥሃል ፧
እስመ ፡ እምህየ ፡ ወፅአ ፡ ሰላም ፡ እምፍጥረተ ፡ ዓለም ፧
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ፍቅር ፡ ክብር ፡ አንድነት ፡ ከጌታ ፡ ተገኝቷልና ፧
፲፭ ፧ ወከመዝ ፡ ይከውን ፡ ለከ ፡ ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ፧
እንደዚሁም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ሁሉም ፡ ይደረግልሃል ፧
ወኵሉ ፡ ይከውን ፡ ወየሐውር ፡ ዲበ ፍኖትከ ፧
ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሥርዓትህ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፧
እንዘ ፡ ጽድቅ ፡ ኢየኀድገከ ፡ ለዓለም ፧
ለዘለዓለሙ ፡ ረድኤት ፡ ሳይርቅህ ፡ ክብር ፡ ሳይለይህ ፧
፲፮ ፧ ወምስሌከ ፡ ይከውን ፡ ማኀደ ሪሆሙ ፧ ወምስሌከ ፡ ክፍሎሙ ፧
የጻድቃን ፡ ማደሪያዎች ፡ ዕድል ፡ ፈንታቸው ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፧
ወእምኔከ ፡ ኢይትሌለዩ ፡ ለዓለም ፡ ወለ ዓለመ ፡ ዓለም ፧
ለዘለዓለሙም ፡ ካንተ ፡ አይለዩም ፧
ወከመዝ ፡ ይከውን ፡ ኑኃ ፡ መዋዕል ፡ ምስለ ፡ ውእቱ ፡ ወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመ ሕያው ፧
ከዚያም ፡ ከአዳም ፡ ልጅ ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋራ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንዲህ ፡ ይሰጣ ቸዋል ።
፲፯ ፧ ወሰላም ፡ ይከውን ፡ ለጻድቃን ፡ ወፍኖቱ ፡ ርቱዕ ፡ ለጻድቃን ፡ በስመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፧
ለወዳጆቹ ፡ ለጻድቃን ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ ይደረግላቸዋል ፧ ሕጉም ፡ በመላእክት ፡ ስም ፡ ላመኑ ፡ ለሕ ጋውያን ፡ ለዘላለሙ ፡ የቀና ፡ ነው ፡ አለኝ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፸፪
### ጉባኤ

፩ ፧ መጽሐፈ ፡ ሚጠተ ፡ ብርሃናተ ፡ ሰማይ ፧
በሰማይ ፡ የሚመላለሱ ፡ የብርሃ ናትን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ መጽ ሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፧
፪ ፧ ፩ዱ ፡ ፩ዱ ዘከመ ፡ ሀለዉ ፡ በበሕዘቢሆሙ ፧
አንዱም ፡ አንዱም ፡ በየወገና ቸው ፡ እንዳሉ ፡ መጠን ፧ የፀ ሐይ ፧ የጨረቃ ፧ አካሔዳቸውን ፡ ሥርዓታቸውን ፡ የሚናገር ፡ መጽ ሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፧
፩ዱ ፩ዱ ፡ በበሥልጣኖሙ ፧
አንዱም ፡ አንዱም ፡ በየምግብ ናቸው ፡ የሚመግቡ ፧
ወበበዘመኖሙ ፧
በየዘመናቸው ፡ የሚመግቡ ፡
፩ዱ ፡ ፩ዱ ፡ በበስሞሙ ፧
አንዱም ፡ አንዱም ፡ በየስማቸው ፡ የሚጠሩ ፧
ወሙላዳቲሆሙ ፧
ሥርቀታቲሆሙ ፡ ሲል ፡ ነው ፧
መውጣታቸውን ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፧

ወበበአውራኂሆሙ ፤
በየወራታቸው ፡ የሚመግቡ ፡ የፀሐይ ፣ የጨረቃ ፣ የከዋክብትን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
እለ ፡ አርአየኒ ፡ ዑርኤል ፡ መልአክ ቅዱስ ፡ ዘሀሉ ፡ ምስሌየ ፤
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያለ ፣ ንጹሕ ፡ ክቡር ፡ የሚሆን ፡ መልአክ ፡ ዑራኤል ፡ ያሳየኝ ፡
ዘውእቱ ፡ መራኂሆሙ ፤
መጋቢያቸው ፡ የሚሆን ፣
፫ ፤ ወኵሉ ፡ መጽሐፎሙ ፡ በከመ፡ ውእቱ ፡ አርአየኒ ፤
ሥርዓቶሙ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ሥርዓታቸውን ፣ ሠሌዳቸውንም ፡ ሁሉ ፡ እንዳሳየኝ ፤
ወበከመ ፡ ኵሉ ፡ ዓመተ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሚመላለሰው ዘመን ፡ ሁሉ ፣ የሚደረገውን ፡ እንዳሳየኝ ፤
እስከ ፡ ይትገበር ፡ ግብር ፡ ሐዲስ ፡ ዘይነብር ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤
እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ እስኪሰጥ ፡ ድረስ ፡ የሚደረገውን፡ እንዳሳየኝ ፡ የፀሐይን ፣ የጨረቃን ፣ የከዋክብትን ፣ አካሄዳቸውን ፣ ሥርዓታቸውን ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ይህ ፡ ለፀሐይ ፣ ለጨረቃ ፣ ለከዋክብት ፡ የወል ፡ ነው ፤

፪ ፤ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ቀዳማዊ ፡ ዘብርሃናት ፤
የፀሐይ ፣ የጨረቃ ፣ የከዋክብት ፣ መጀመርያው ፡ ሥርዓት ፡ ይህ ፡ ነው ፤
፭ ፤ ፀሐይ ፡ ብርሃን ፡ ሙፃኡ ፡ በኆዋኀወ ፡ ሰማይ ፡ እለ ፡ መንገለ ፡ ጽባሕ ፣
ለብሩህ ፡ ፀሐይ ፡ ሲል ፡ ነው ፣ የብሩህ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫው ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ ሰማይ ፡ ኆዋኀው ፡(መስኮቶች ፡) ነው ፤
ወምዕራቢሁ ፡ በኆዋኀወ ፡ ሰማይ ፡ ዘምዕራብ ፤
መግቢያውም ፡ በምዕራብ ፡ ባሉ በሰማይ ፡ መስኮቶች ፡ ነው ፤
፮ ፤ ወርኢኩ ፡ ስሱ ፡ ኆዋኀው ፡ እለ፡ እምኀበ ፡ ይወፅእ ፡ ፀሐይ ፤
እምኀቤሆሙ ፡ ይወጽእ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ፀሐይ ፡ የሚወጣባቸው ፮ቱን ፡ ኆዋኀው ፡ አየሁ ፤
ወስሱ ፡ ኆዋኀው ፡ እለ ፡ ኀበ ፡ የዐርብ ፡ ፀሐይ ፣
ፀሐይ ፡ የሚገባባቸው ፡ ፮ቱን ፡ ኆዋኀው (መስኮቶች) ፡ አየሁ ፤ (ኆኀት ፡ አንቀጽ ፡ መስኮት ፡ አርእስት ፡ ነው ፡) ይላል ፤
፯ ፤ ወወርኅ ፡ በውእቶን ፡ ኆዋኀው ፡ ይሠርቅ ፡ ወየዐርብ ፤
ጨረቃም ፡ በእነዚያ ፡ ኆዋኀው፡ (መስኮቶች፡) ይወጣል ፤ ይገባል ፤
፰ ፤ ወመራሕያኒሆሙ ፡ ለከዋክብተ፡ ሰማይ ፡ ምስለ ፡ እለ ፡ ይመርሕዎሙ ፤
የወር፡ መጋቢዎችን ፡ የሚመሩ ፡

የዘጠና ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ መጋቢ ዎች ፡ከሚመሯቸው ፡ ከወር ፡ መጋቢዎች ፡ ጋራ ፡ ይወጣሉ ፤ ይገባሉ ፤ አንድም ፡ የሺሕ ፡ አለ ቆችን ፡ የሚመሩ ፣ የወር ፡ መጋ ቢዎች ፡ ከሚመሯቸው ፡ ከሺሕ፡ አለቆች ፡ ጋራ ፡ ይወጣሉ ፣ ይገ ባሉ ፤ አንድም ፡ የዕለት፡ መጋቢ ዎችን ፡ የሚመሩ ፣ የሺሕ ፡ አለቆች ፡ ከሚመሯቸው ፣ ከዕ ለት ፡ መጋቢዎች ፡ ጋራ ፡ በነ ዚህ ፡ በ፷ቱ ፡ ኀዋኀው ፡ (መስ ኮቶች) ፡ ይወጣሉ ፣ ይገባሉ ፤

፷ቱ ፡ በጽባሕ ፡ ወ፷ቱ ፡ በምዕራብ ፡ ፀሐይ ፤

፷ቱ ፡ ኀዋኀው ፡ (መስኮቶች) ፡ በምሥራቅ ፣ ፷ቱ ፡ ኀዋኀው ፡ (መስኮቶች)፡በምዕራብ ፡ ናቸው፤

፱ ፤ ወኵሎሙ ፡ ፩ዱ ፡ ፩ዱ ፡ እም ድኅረ ፡ ካልኡ ፡ ርቱዕ ፤

አንዱንም ፡ አንዱን ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ያየሁት ፡ አንዱም ፡ አን ዱም፡ የቀና ፡ የጸና ፡ ነው፤

ወመሳክው ፡ ብዙኃት ፡ እምየማኑ ፡ ወእምፀጋሙ ፡ ለዝኩ ፡ ኆኅት ፣

በዚህ ፡ ኆኅት ፡ /መስኮት/ ፡ በቀ ኙም ፣ በግራውም ፡ ብዙ ፡ ኀዋ ኀው ፡ /መስኮቶች/ ፡ አሉ ፣ ዝኩ ያለው ፡ የሚያዝያን ፡ ኆኅት ፡ ነው ፤ ፀሐይ ፡ የተፈጠረ ፡ በሚያዝያ ፡ ኆኅት ፡ ነውና ፤ እምየማኑ ፣ ወእምፀጋሙ ፡ አለ፤ በቀኝ ፣ የግንቦት ፣ የሰኔ ፣ በግራ ፣ የመጋቢት ፣ የየካቲት ፣ የጥር ፣ ኆኅት ፡ አለና ፤

፲ ፤ ወቀዳሚ ፡ ይወፅእ ፡ ብርሃን ፡ ዘየዐቢ ፡ ዘስሙ ፡ ፀሐይ ፣

ስሙ ፡ ፀሐይ ፡ የሚባል ፡ ከጨ ረቃ ፡ የሚበልጥ ፡ ፀሐይ ፡ መጀ መሪያ ፡ ይወጣል ፤

ወክበቡ ፡ ከመ ፡ ክበበ ፡ ሰማይ ፣

ሰሌዳውም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ሰሌዳ ፡ ነው ፤

ወኵለንታሁ ፡ ምሉዕ ፡ እሳተ ፡ ዘያበ ርህ ፡ ወያውዒ ፤

የማያበራ ፡ እሳት ፡ አለና፡ ሁሉን ተናው ፡ የሚያበራና ፡ የሚያቃ ጥል፡ እሳት ፡ ነው ፤

፲፩ ፤ ወሠረገላተ ፡ በኀበ ፡ የዐርግ ፡ ነፋስ ፡ ይነፍሕ ፣

ወደሠረገላው ፡ በሚወጣበት ፡ ጊዜ ፣ ነፋስ ፡ ይነፍሳል ፤ ሠረ ገላ ፡ የሚለው ፡ ርጉዕ ፡ ነፋስን ፡ ነው ፤ ይነፍሕ፡የሚለው፡ዝርው፡ ነፋስን፡ነው ፣ ሠረገ ላውን፡የሚ ያፋጥን፡ነው ፣ አድማስን ፡በምሥ ራቅ ፡ ከ፮ ላይ፣ በምዕራብ፡ ከ፮ ፡ ላይ ፡ ቀዶታል፤

፲፪ ፤ ወየዐርብ ፡ ፀሐይ ፡ እምሰማይ ፡ ወይገብእ ፡ እንተ ፡ መስዕ ፣

ፀሐይም ፡ ከምሥራቅ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ይገባል ፤

ከመ ፡ ይሑር ፡ ምሥራቀ ፡ ወይት መራሕ ፡ ከመ ፡ ይባዕ ፡ ኅበ ፡ ዝኩ ፡ ኆኅት ፤ ወያበርህ ፡ በገጸ ፡ ሰማይ ፤

ፀሐይ ፡ ስታበራ ፡ ውላ ፤ በምዕ ራብ ፡ ገብታ ፤ በሰሜን ፡ ዙራ ፤ በምሥራቅ ፡ ትወጣለች፤ ይህስ ፡ ከኆኅቱ ፡ ስትደርስ ፡ መዓልትና ፡ ሌሊት ፡ ይፈራረ ቃል ፡ ብሎ ፤ አድማስ ፡ እንደ ሲኦሎ ፡ መዝጊያ ፤ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ መወርወሪያ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ በዚያ ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ ፡ ትሄዳለች ፤ ይህም ፡ አይበዛም ፡ እንጂ ፤ ሌሊትና ፡ መዓልት ፡ ይፈራረቃል ፡ ብሎ ፡ ኆኅት ፡ ማለቱ ፡ ስለወጣ በት ፤ ስለ ፡ ገባበት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ፈሰስ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ ናጌብ፡ እንደ ፡ ወጋግራ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ አድማስ ፡ እንደ ፡ ግድግዳ ፡ ነው ፤ በፈሰሱ ፡ ዙሪያ ፡ በምሥራቅ ፡ ትወ ጣለች ፤ ብርሃኑን ፡ ናጌብ ፤ ዋዕ ዩን ፡ ውቅያኖስ ፡ ይከለክለዋል ፤

ወየዐርብ ፡ ፀሐይ ፡ እምሰማይ ፤

ከሰማይ ፡ ይርቃል ፤ አንድም ፡ በሰማይ ፡ ይገባል ፤ በኆኅት ፡ ዓባይ ፡ የሚያዝያ ፡ ኆኅት ፡ ከአምስቱ ፡ ኆኅት ፡ በልጦ ፡ አይደለም ፤ ዓባይ ፡ ማለቱ ፤ ፀሐይ ፡ የተፈጠረ ፡ በሚያዝያ ፡ ኆኅት ፡ ነውና ፤

ዐሥሩ ፡ ወጀቱ መሳከው ፡ ርኅዋት ፤

በአንዱ ፡ የሁሉን ፡ መናገር ፡ ነው ፤ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ የተዘረጋ ፡ ስልሣ ፡ ከንትሮስ ፡ አለ ፤ በዚያ ፡ አልፎ አልፎ ፡ ርጉዕ ፡ ነፋስ ፡ አለ ፤ ፀሐይ ፡ የምታርፍ በት ፡ ነው ፤ ለዚያ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ነዋኅው ፡ አለው ፤ አን ድም ፡ እንደ ፡ ግርግሪያ ፡ ያለ ፡ ከፀሐይ ፡ የሚለይ ፡ ነው ፤ ለእርሱ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ኃዋኅው ፡ አሉት ፤ በዚያ ፡ ብርሃን ፡ ፀሐይ ፡ ለእኛ ፡ ይመግበናል ፤

፲፫ ፤ ወከመዝ ፡ ይወፅእ ፡ በወርኀ ፡ ቀዳማዊ ፡ በኆኅት ፡ ዓባይ ፤

አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገርኩት ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በታላቁ ፡ መስኮት ፡ ይወጣል ፤

ወይወጽእ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ ራብዕት ኆኅት ፡ እምእልኩ ፡ ፮ቱ ፡ ነዋኅው ፤ እለ ፡ መንገለ ፡ ምሥራቀ ፡ ፀሐይ ፤

ባራተኛውም ፡ ደጃፍ ፡ ይወጣል፤ ይህችውም ፡ አራተኛዪቱ ፡ ደጃፍ ፀሐይ ፡ በምሥራቅ ፡ ከሚወጣ ባቸው ፡ ከስድስቱ ፡ ደጃፎች ፡ አንዲቱ ፡ ናት፤

፲፬ ፤ ወበይእቲ ፡ ራብዕት ፡ ኆኅት ፡ እንተ ፡ እምኔሃ ፡ ይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡

በወርኀ ፡ ቀዳማዊ ፡ ባቲ ፡ ዐሡሩ ፡ ወክልዔ ፡ መሳክው ፡ ርኅዋት ፡ ዘእም ኔሆን ፡ ይወፅእ ፡ ላህብ ፡ ሶበ ፡ ይትረኀዉ ፡ እምዘመነ ፡ ዚአሆሙ ፡

በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ፀሐይ ፡ ከእርሷ ፡ ከሚወጣባት ፡ በዚያ ችም ፡ በአራተኛዪቱ ፡ ደጃፍ ፡ በዘመናቸው ፡ በሚከፈቱበት ፡ ጊዜ ፡ ከእነርሱ ፡ ዋዕይ ፡ የሚ ወጣባቸው ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ደጃፎች ፡ አሉባት ፡

የሚዘጉበት ፡ ጊዜ ፡ ነገሮ ፡ አይ ደለም ፡ በዘመናቸው ፡ ለሰው ፡ በሚያበሩበት ፡ በሚመግቡበት ፡ ጊዜ ፡ ሲል ፡ ነው ፡

፲፫ ፡ ሶበ ፡ ይሠርቅ ፡ ፀሐይ ፡ እም ሰማይ ፡ ይወፅእ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ ራብዕት ፡ ኆኅት ፡ ሠላሳ ፡ ጽባሐ ፡

ፀሐይ ፡ ከምሥራቅ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ በዚያች ፡ ባራተኛዪቱ ፡ ደጃፍ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ይወጣል ፡

፲፬ ፡ ወበራብዕት ፡ ኆኅት ፡ እንተ ፡ እምዕራብ ፡ ሰማይ ፡ ርቱዐ ፡ ይወርድ ፡

በገጸ ፡ ሰማይ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ በሰ ማይ ፡ ካለው መግቢያ ፡ ባራተኛ ዪቱ ፡ ደጃፍ ፡ ሲያበራ ፡ ውሎ ፡ አቅንቶ ፡ ይገባል ፡

፲፭ ፡ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ትነ ውኅ ፡ ዕለት ፡ እምዕለት ፡ ወተሐጽር ሌሊት ፡ እምሌሊት ፡ እስከ ፡ ፴ ጽባሕ ፡

በእነዚያ ፡ ወራቶች ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ቀኒቱ ፡ ከቀን ፡ ትረዝማለች ፡ ሌሊቲቱም ፡ ከሌ ሊት ፡ ታጥራለች ፡ እለ ፡ የሚ ያዝያ ፡ ዕለት ፡ ከመጋቢት ፡ ዕለት ፡ ትበልጣለች ፡ አንድም ፡ ከየካቲት ፡ ዕለት ፡ የሚያዝያ ፡ ዕለት ፡ ይበ ልጣል ፡ ብተትም ፡ የሚያዝያ ፡ ኆኅትም ፡ የሚያዝያ ፡ ነው ፡

፲፮ ፡ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ትነውኅ ፡ ካዕበተ ፡ ዕለት ፡ እምሌሊት ፡

በዚህችም ፡ ቀን ፡ ቀኒቱ ፡ ከሌ ሊቱ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ ትበልጣ ለች ፡ ከሚያዝያ ፡ ሌሊት ፡ የሚ ያዝያ ፡ ዕለት ፡ ትበልጣለች ፡

፲፱ ፡ ወትከውን ፡ ዕለት ፡ ጥንቁቀ ፡ ዐሠርተ ፡ ክፍለ ፡

ጠንቅቀው ፡ ቢቈጥሯት ፡ ቀኒቱ ፡ ዐሥር ፡ ክፍል ፡ ትሆናለች ፡

ወሌሊት ፡ ትከውን ፡ ስመንተ ፡ ክፍለ ፡

ሌሊቲቱም ፡ ስምንት ፡ ክፍል ፡ ትሆናለች ፡

፳ ፡ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ እምይእቲ ፡ ራብዕት ፡ ኆኅት ፡

ፀሐይም ፡ ከዚህች ፡ ከአራተኛዪቱ ደጃፍ ፡ ይወጣል ፡

ወየዐርብ ፡ በራብዕት ፡ ኆኅት ፡

በአራተኛዪቱም ፡ ደጃፍ ፡ ይገባል ፡

፳፩ ፡ ወይገብእ ፡ ውስተ ፡ ሐምስት ፡ ኆኅት ፡ እንተ ፡ ጽባሕ ፡ ፴ ፡ ጽባሐ ፡

ሠላሳ ፡ ቀን ፡ በምሥራቅ ፡ ወዳ ለችው ፡ ወደ ፡ አምስተኛዪቱ ፡ ደጃፍ ፡ ይመሳስሳል ፤

ወይወፅእ ፡ እምኔሃ ፡ ወየዐርብ ፡ ውስተ ፡ ሐምስት ፡ ኖኅት ፤

ከእርሷም ፡ ወጥቶ ፡ በአምስተኛ ዪቱ ፡ ደጃፍ ፡ ይገባል ፤ ኖኅት ፡ ይለወጣል ፤ ኖኅትም ፡ የግንቦት ፡ ብተትም ፡ የግንቦት ፡ ነው ፤

፰፪ ፤ ወእሜሃ ፡ ትነውኅ ፡ ዕለት፡ ፪ተ ፡ እደ ፤

የግንቦት ፡ ዕለት ፡ ከመጋቢት ፡ ዕለት ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ ትበልጣ ለች ፤

ወትከውን ፡ ዕለት ፡ ዐሠርተ ፡ ወአ ሐደ ፡ ክፍለ ፤

ቀኒቱም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ክፍ ልን ፡ ትሆናለች ፤

ወተሐጽር ፡ ሌሊት ፡ ወትከውን ፡ ፯ተ ፡ ክፍለ ፤

ሌሊቲቱም ፡ ታጥራለች ፤ ሰባት ፡ ክፍልንም ፡ ትሆናለች ፤

፰፫ ፤ ወይገብእ ፡ ፀሐይ ፡ ለጽባሕ ፤ ፀሐይም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለሳል ፤

ወይበውእ፡ ውስተ ፡ ሳድስት፡ ኖኅት፤ ወደስድስተኛዪቱም፡ ደጃፍ ፡ ይገ ባል፤ ኖኅት ፡ ይለውጣል ፤ ኖኅ ትም ፡ የሰኔ ፤ ብተትም ፡ የሰኔ ነው ፤ በሰኔ ፡ በስድስተኛው ፡ ኖኅት ፡ ይወጣል ፤

ወይወፅእ ፡ ወየዐርብ ፡ በሳድስት ፡ ኖኅት ፡ ፴ ፡ ወ፩ደ ፡ ጽባሐ ፤

ሚያዝያ ፤ ግንቦት ፤ ሰኔ ፤ ሲያ ልቅ ፡ አንድ ፡ ጳጉሜን ፡ አለ ችና ፤

በእንተ ፡ ትእምርተ ፡ ዚአሃ ፤

የጳጉሜን ፡ ቀን ፡ ከእርሷ ፡ ጋራ፡ ስለኖረች ፤ በስድስተኛዪቱ፡ ደጃፍ፡ ሠላሳ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ይወጣል ፤ ይገባል ፤

፰፬ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ትነውኅ ፡ ዕለት ፡ እምሌሊት ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ቀኒቱ ፡ ከሌ ሊቲቱ ፡ ትረዝማለች ፤

ወትከውን፡ ዕለት ፡ ካዕበተ ፡ ሌሊት ፤ ቀኒቱም ፡ የሌሊቲቱ ፡ እጥፍ ፡ ትሆናለች፤

ወትከውን፡ ዕለት፡ ፲ተወ፪ተ፡ ክፍለ ፤ ቀኒቱም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክፍልን ፡ ትሆናለች ፤

ወተሐጽር ፡ ሌሊት ፡ ወትከውን ፡ ስድስተ ፡ ክፍለ፤

ሌሊቲቱም ፡ አጥራ ፡ ስድስት ፡ ክፍልን ፡ ትሆናለች ፤

፰፭ ፤ ወይትነሣእ ፡ ፀሐይ ፡ ከመ ፡ ትሕጽር ፡ ዕለት ፡ ወትኑኅ ፡ ሌሊት፤ ይትመየጥ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ቀኑ ፡ ያጥር ፡ ዘንድ ፤ ሌሊቲቱ ፡ ትረዝም፡ ዘንድ ፡ ፀሐይ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ ይመለሳል ፤ ማለት፡ ዓውዱን ፡ ይለውጣል ፤

፷፮ ፤ ወይገብእ ፡ ፀሐይ ፡ ለጽባሕ ፡ ወይበውእ ፡ ውስተ ፡ ሣድስት ፡ ኆኅት ፤

ብተት ፡ የሐምሌ፣ ኆኅት ፡ የሰኔ ፤ መተካከል ፡ ከግንቦት ፡ ነው ፤ ምነው ፡ ብተት ፡ የሐምሌ ፣ ኆኅት ፡ የሰኔ ፡ ከሆነ ፣ መተካከሉ ፡ ከግንቦት ፡ መሆኑ ? ቢሉ ፣ ከኬክሮሱ ፡ ያንዱ ፡ ኆኅት ፡ ፴ው ፡ ረጅም ፤ ሠላሳው ፡ አጭር ፡ ነው ፣ በረጅሙ ፡ ኆኅት ፡ ስትሄድ ፡ ይረዝማል ፣ ባጭሩ ፡ ኆኅት ፡ ስትሄድ ፡ ያጥራልና ፤ አንድም ፡ እንደ ፡ አኅበር ፡ ፴ው ፡ እንደዝሐ ፡ ያለ ፡ ነው ፣ እንደ ፡ አኅበር ፡ ባለው ፡ከንትሮስ ፡ ስትሄድ ፡ ይረዝማል፣ እንደዝኃ ፡ ባለው ፡ ስትሄድ፡ ያጥራልና ፤ አንድም ፡ ጠፈር ፡ እንደ ፡ ቤተ ፡ ንጉሥ ፡ ያለ ፡ ነው፣ በማእከለ ፡ ሰማይ ፡ ስትሄድ ፡ ይረዝማል ፤ በጽንፈ ፡ ሰማይ ፡ ስትሄድ ፡ ያጥራልና ፤

ወይሠርቅ ፡ እምኔሃ ፡ ወየዓርብ ፡ ሠላሳ ፡ ጽባሐ ፤

ከእርሷ ፡ ይወጣል ፤ ሠላሳ ፡ ቀን፡ በምዕራብ ፡ ይገባል ፤

፷፯ ፤ ወሶበ ፡ ተፈጸመ ፡ ሠላሳ ፡ ጽባሕ ፡ ተሐጽጽ ፡ መዓልት ፡ ወትከውን ፡ አሐደ ፡ ክፍለ ፡ ጥንቁቀ ፤

ሠላሳውም ፡ ቀን ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ጠንቅቆ ፡ ቢቈጥሩ ፡ ቀኒቱ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ ትጐድላለች ፤

ወትከውን ፡ ዕለት ፡ ዐሠርተ ፡ ወአሐደ ፡ ክፍለ ፡ ወሌሊት ፡ ሰብዓተ ፡ ክፍለ ፤

ቀኒቱ ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ክፍል ትሆናለች ፤ ሌሊቲቱም ፡ ሰባት ፡ ክፍል ፡ ትሆናለች ፤

፷፰ ፤ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ እምነ ፡ ምዕራብ ፡ እምይእቲ ፡ ሳድስት ፡ ኆኅት ፡ ወየሐውር ፡ ምሥራቀ ፣

ፀሐይም ፡ ከስድስተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ከምዕራብ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ምሥራቅ ፡ ይሄዳል ፤

ወይሠርቅ ፡ በኃምስት ፡ ኆኅት ፡ ሠላሳ፡ ጽባሐ ፤ ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ ካዕበ፡ በሐምስት፡ ኆኅት ፡ እንተ ፡ ምዕራብ ፤

ሠላሳም ፡ ቀን ፡ በአምስተኛዪቱ መስኮት ፡ ይወጣል ፤ በሚገባባት ባምስተኛዪቱ ፡ መስኮት፡ ዳግመኛ በመግቢያው ፡ ይገባል ፤ ኆኅት ፡ ይለወጣል ፣ ብተት ፣ የነሐሴ፣ ኆኅት ፡ የግንቦት ፤ መተካከል ፡ ከሚያዝያ ፤

፷፱ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ተሐጽር ፡ ዕለት ፡ ፪ተ ፡ ክፍለ ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ቀኒቱ ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ታንሣለች ፣ ሁለት ፡ ክፍል፡ ማጠሯ ፡ ከሰኔ ፡ ነው ፡ እንጂ ፣ ከሐምሌ አይደለም ፤

ወትከውን ፡ ዕለት ፡ ዐሠርተ ፡ ክፍለ ፡
ወሌሊት ፡ ሰመንተ ፡ ክፍለ ።
ቀኒቱም ፡ ዐሥር ፡ ክፍል ፡ ትሆ
ናለች ፤ ሌሊቲቱም ፡ ስምንት ፡
ክፍል ፡ ትሆናለች ።

፴ ፡ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ እምይእቲ ፡
ሐምስት ፡ ኆኅት ፡
ፀሐይም ፡ ከዚያች ፡ ካምስተኛዪቱ፡
መስኮት ፡ ይወጣል ፤
ወየዐርብ ፡ በሐምስት ፡ ኆኅት ፡ እንተ
ምዕራብ ።
በሚገባባት ፡ ባምስተኛዪቱ ፡ መስ
ኮት ፡ ይገባል ።

፴፩ ፡ ወይሠርቅ ፡ በራብዕት ፡ ኆኅት ፤
ብተት ፡ የመስከረም ፤ ኆኅት ፡
የሚያዝያ ፤ መተካከል ፡ ከመ
ጋቢት ።

፴ወ፩፪ ፡ ጽባሐ ።
ሐምሌ ፡ ነሐሴ ፡ መስከረም ፡
ሲያልቅ ፤ አንድ ፡ ጳጕሜን ፡
አለና ፤
በእንተ ፡ ትእምርተ ፡ ዚአሃ ፡ ወየዐ
ርብ ፡ በምዕራብ ።
የጳጕሜ ፡ ቀኗ ፡ ገብታ ፡ ስለ ፡
ተቆጠረች ፡ በአራተኛዪቱ መስ
ኮት፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ይወ
ጣል ፤ በመግቢያዋም ፡ ይገባል ።

፴፪ ፡ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ይትዔረይ ፡
መዓልት ፡ ምስለ ፡ ሌሊት ።
በዚያችም ፡ ቀን ፡ ቀኑ ፡ ከሌ
ሊቱ ፡ ጋራ ፡ ይተካከላል ።

ወይከውን ፡ ዕሩየ ።
ከሐምሌ ፡ ጀምሮ ፡ ሌሊቱ ፡
ሲወጣ ፤ መዓልቱ ፡ ሲወርድ ፤
መዓልቱና ፡ ሌሊቱ ፡ ይተካከ
ላል ።

ወትከውን፡ ሌሊት ፡ ተሰዓተ ፡ ክፍለ፤
ወመዓልት ፡ ተሰዓተ ፡ ክፍለ ።
ሌሊቲቱ ፡ ዘጠኝ ፡ ክፍል ፤ ቀኒ
ቱም ፡ ዘጠኝ ፡ ክፍል ፡ ትሆ
ናለች ።

፴፫ ፡ ወይወጽእ ፡ ፀሐይ ፡ እም
ይእቲ ፡ ኆኅት ፤
ፀሐይም ፡ ከዚያች ፡ ካራተኛዪቱ
መስኮት ፡ ይወጣል ።
ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ ወይገብእ ፡
ለጽባሕ ፤
በመግቢያውም ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡
ምሥራቅ ፡ ይመለሳል ።

፴፬ ፡ ወይወጽእ ፡ በሣልስት ፡ ኆኅት
ሠላሳ ፡ ጽባሕ ፤
ብተት ፡ የጥቅምት ፤ ኆኅት ፡
ይለውጣል ፤ ኆኅት ፡ የመጋቢት፡
መተካከል ፡ ከየካቲት ፤ በሦስተ
ኛውም ፡ መስከት ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡
ይወጣል ፤
ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ በሣልስት ፡
ኆኅት ።
በሦስተኛውም ፡ መስኮት ፡ በምዕ
ራብ ፡ ይገባል ።

፲፭ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ትነውኅ ፡ ሌሊት ፤እምሌሊት ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ጽባሕ ፤ ወተሐጽር ፡ ዕለት ፡ እም ዕለት ፡ እስከ ሠላሳ ፡ ዕለት ፤
በዚህችም ፡ ቀን ፡ አንዲቱ ፡ ሌሊት ፡ ከአንዲቱ ፡ ሌሊት ፤ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ትበልጣለች ፤ አንዲቱም ፡ ቀን ፡ ከአንዲቱ ፡ ቀን ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ታጥራለች ፤
ወይከውን ፡ ሌሊት ፡ ዐሠርተ ፡ ክፍለ ጥንቁቀ ፡ ወመዓልት ፡ ሰመንተ ፡ ክፍለ ፤
ጠንቅቆ ፡ ቢቆጥሩት ፡ ሌሊቱም ዐሥር ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ፤ ቀኑም ፡ ስምንት ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ፤ የጥቅምት ፡ ሌሊት ፡ ከመስከረም ፡ ሌሊት ፡ ትበልጣለች ፤ አንድም ፡ ከነሐሴ ፡ ሌሊት ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ትበልጣለች ፤
፲፮ ፤ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ እምይእቲ ፡ ሣልስት ፡ ኆኅት ፤
ፀሐይም ፡ ከዚያች ፡ ከሦስተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ወጥቶ ፤
ወየዐርብ ፡ በሣልስት ፡ ኆኅት ፤ ወየዐርብ ፡ ወይገብእ ፡ ውስተ ፡ ምሥራቅ፤ በምዕራብ ፡ ባለ ፡ በሦስተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ይገባል ፤ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ ይመለሳል ፤

፲፯ ፤ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ ውስተ ፡ ካልዕት ፡ ኆኅት ፡ እምሥራቅ ፡ ሠላሳ ፡ ጽባሐ ፤
ፀሐይም ፡ በሁለተኛው ፡ መስኮት ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ከምሥራቅ ፡ ይወጣል ፤
ኆኅት ፡ ይለወጣል ፤ ብተት ፡ የኅዳር ፤ ኆኅት ፡ የየካቲት ፤ መተካከል ፡ ከጥር ፤
ወይገብእ ፡ በምሥራቅ ፤
ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለሳል ፤
፲፰ ፤ ወከመዝ ፡ የዐርብ ፡ በካልእ ፡ ኆኅት ፡ በምዕራብ ፡ ሰማይ ፤
እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ በሁለተኛው ፡ መስኮት ፡ በሰማይ ፡ ባለ ፡ መግቢያው ፡ ይገባል ፤
ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ትከውን ፡ ሌሊት ዐሠርተ ፡ ወአሐደ ፡ ክፍለ ፡ ወዕለት ሰብዓተ ፡ ክፍለ ፤
በዚያችም ፡ ቀን ፡ ሌሊቲቱ ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ክፍልን ፤ ቀኒቱም ፡ ሰባት ፡ ክፍልን ፡ ትሆናለች ፤
፲፱ ፤ ወይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፡ እምይእቲ ፡ ካልዕት ፡ ኆኅት ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ በካልዕት ፡ ኆኅት ፤
ፀሐይም ፡ በዚህች ፡ ቀን ፡ ከዚህች ፡ ከሁለተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ወጥቶ ፡ በሁለተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ይገባል ፤

ወይገብእ ፡ በምሥራቅ ፤
ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለሳል ፤
ብተት ፡ የታኅሣሥ ፤ ኆኅት ፡
የጥር ፤ መተካከል ፡ ለባሕቲቱ ፡
ለብቻው ፡ ነው ፤
፵ ፤ ወይወፅእ ፡ በእሐቲ ፡ ኆኅት ፡
፴ወ፩ደ ፡ ጽባሐ ፤
ጥቅምት ፤ ኅዳር ፤ ታኅሣሥ ፡
ሲያልቅ ፡ አንዲት ፡ ጳጕሜን ፡
አለችና ፤
በእንተ ፡ ትእምርተ ፡ ዚአሃ ፤
የጳጕሜን ፡ ቀኗ ፡ ገብታ ፡ ስለ ፡
ተቈጠረች ፤ፀሐይም ፡ ባንዲቱ ፡
በዚህች ፡ (ጥር) ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡
ቀን ፡ ወጥቶ ፤
ወየዓርብ ፡ በምዕራብ ፡ በእሐቲ ፡
ኆኅት ፤
በዚህች ፡ በአንዲቱ ፡ መስኮት ፡
በምዕራብ ፡ ይገባል ፤
፵፩ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ትነውኅ ፡
ሌሊት ፤
በዚያችም ፡ ቀን ፡ ሌሊቲቱ ፡
ከቀኒቱ ፡ ትረዝማለች ፤
ወትከውን ፡ ካዕበታ ፡ ለዕለት ፤
ቀኒቱም ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ ትሆ
ናለች ፤
ወትከውን ፡ሌሊት ፡፲ተ ወ፪ተ፡
ክፍለ ፡ ጥንቁቀ ፤
ጠንቅቆ ፡ ቢቆጥሩ ፤ ሌሊቲቱ ፡
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክፍልን ፡ ትሆ
ናለች ፤
ወመዓልት ፡ ስድስተ ፡ ክፍለ ፤

ቀኒቱም ፡ ስድስት ፡ ክፍልን ፡ ትሆ
ናለች ፤
፵፪ ፤ ወፈጸመ ፡ ፀሐይ ፡ አርእስ
ቲሁ ፤
ሥርቀታቲሁ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ይህም ፡ ዓለም ፡ እስኪያልፍ ፡
ድረስ ፡ ሲወጣ ፤ ሲገባ ፤ ይኖ
ራል ፤ ብሎ ፡ ሑረታቲሁ ፡ ሲል ፡
ነው ፤ ይህም ፡ ዓለም ፡ እስኪያ
ልፍ ፡ ድረስ ፡ ሲሄድ ፡ ይኖራል ፡
ብሎ ፤ ኅዋኅዊሁ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ኆኅቱን ፡ ጨረሰ፡እንግዲህ ፡ በገጸ ፡
ሰማይ ፡ ሲያበራ ፡ ውሎ ፤ በምዕ
ራብ ፡ ገብቶ ፤ በሰሜን ፡ ዙሮ ፡
በምሥራቅ ፡ እየወጣ ፤ ሲመላ
ለስ ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡
ኆኅት ፡ አይለውጥምና ፤
ወዳግመ ፡ የዐውድ ፡ ዲበ ፡ እሉ ፡
አርእስቲሁ ፤
ዳግመኛም ፡ በእኒህ ፡ መስኮቶች ፡
ላይ ፡ ዙሮ ፡ በጥር ፡ ኅዋኅው ፡
ይገባል ፤ ብተትም ፡ የጥር ፤
ኆኅትም ፡ የጥር ፡ ነው ፤
ወቦአ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ ኆኅት ፤
ወደ ፡ ሁለተኛውም ፡ በር ፡ ገባ ፤
ብተትም፡ የየካቲት ፤ ኆኅትም ፡
የየካቲት ነው ፤
ወይበውእ ፡ በውእቱ ፡ ኆኅት ፡ ፴ ጽባሐ፡
ወበምዕራብኒ ፡ በእንጻሪሁ ፡ የዓርብ ፤

ሠላሳ ፡ ቀን ፡ በዚያ ፡ በመግቢያው ፡ መስኮት ፡ በትክክል ፡ ይገባል ፤ ጥር ፤ የካቲት ፤ መጋቢት ፡ ሲያልቅ ፡ አንድ ፡ ጳጉሜን ፡ አለና ፤

፸፫ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ተሐፅር ፡ ሌሊት ፡ እምኑኀ ፡ አሐደ ፡ እደ ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ሌሊቲቱ ፡ ከርዝመቷ ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ ታጥራለች ፤

ዝ ፡ ውእቱ ፡ ክፍል ፡ አሐዱ ፡ ወትከውን ፡ ሌሊት ፡ ዐሠርተ ፡ ወአሐደ ፡ ክፍለ ፡ ወመዓልት ፡ ሰብዓተ ፡ ክፍለ ፤

ይኸውም ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ ነው ፤ ሌሊቲቱ ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፤ ቀኒቲቱም ፡ ሰባት ፡ ክፍል ፡ ትሆናለች ፤

፸፬ ፤ ወገብዐ ፡ ፀሐይ ፤ ወቦአ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ ኆኅት ፡ እንተ ፡ ምሥራቅ ፤

ፀሐይም ፡ ተመልሶ ፡ በምሥራቅ ፡ ወደሚወጣበት ፡ ወደሁለተኛው ፡ መስኮት ፡ ገባ ፤

ወይገብእ ፡ ዲበ ፡ ዝኩ ፡ አርእስቲሁ ሠላሳ ፡ ጽባሐ ፡ ይሠርቅ ፡ ወየዐርብ ፤

በዚህም ፡ መስኮት ፡ ተመልሶ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ይወጣል ፡ ይገባል ፤

፸፭ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ተሐጽር ፡ ሌሊት ፡ እምኑኃ ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ሌሊቲቱ ፡ ከርዝመቷ ፡ ታጥራለች ፤

ወትከውን ፡ ሌሊት ፡ ዐሠርተ ፡ ክፍለ ፡ ወመዓልት ፡ ሰመንተ ፡ ክፍለ ፤

ሌሊቲቱ ፡ ዐሥር ፡ ክፍል ፤ ቀኒቱም ፡ ስምንት ፡ ክፍል ፡ ትሆናለች ፤

፸፮ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ይወፅእ ፡ ፀሐይ ፡ እምይእቲ ፡ ካልእት ፡ ኆኅት ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ፀሐይ ፡ ከዚያች ፡ ከሁለተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ይወጣል ፤

ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ ወይገብእ ፡ ምሥራቀ ፤

በመግቢያውም ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለሳል ፤

፸፯ ፤ ወይሠርቅ ፡ በሣልስት ፡ ኆኅት ፡ ሠላሳ ፡ ወአሐደ ፡ ጽባሐ ፡ በእንተ ፡ ትእምርተ ፡ ዚአሃ ፤

ፀሐይም ፡ የጳጉሜን ፡ ቀን ፡ ገብታ ፡ ስለተቈጠረች ፤ በሦስተኛዪቱ ፡ መስኮት ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ወጥቶ ፤

ወየዐርብ ፡ በምዕራብ ፡ ሰማይ ፤

በሰማይ ፡ ባለ ፡ መግቢያው ፡ ይገባል ፤

፸፰ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ተሐጽር ፡ ሌሊት ፤ ወትከውን ፡ ተሰዓተ ፡ ክፍለ ፤

በዚያችም ፡ ቀን ፡ ሌሊቲቱ ፡ ታንሳለች ፤

ወዕለት ፡ ትከውን ፡ ተሰዓተ፡ ክፍለ ።
ሌሊቲቱም ፡ ዘጠኝ ፤ ቀኒቱም ፡
ዘጠኝ ፤ ክፍል ፡ ትሆናለች ።
፵፱ ፡ ወይትዔረይ ፡ ሌሊት ፡ ምስለ ፡
መዓልት ።
ከጥር ፡ ጀምሮ ፡ መዓልቱ ፡
ሲወጣ ። ሌሊቱ ፡ ሲወርድ ፡
ከቀኑ ፡ ጋራ ፡ ይተካከላል ፤
ወይከውን ፡ ዓመት ፡ ጥንቁቀ ፡
መዋዕለ ፡ ሠለስተ ፡ ምእተ ፡ ወስድሳ፡
ወረቡዐ ፤
ዓመቱንም ፡ ጠንቅቆ ፡ ቢቈጥሩት፡
ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አራት
ቀን ፡ ይሆናል ፤ ፯ኛዪቱን ፡ ቀን ፡
ተዋት ። ከሱባዔ ፡ ትርፍ ፡
ከሆነች ፡ ብሎ ።
፶ ፡ ወኑኃ ፡ ለዕለት ፡ ወለሌሊት ፡
ወሕፀራ ፡ ለዕለት ፡ ወለሌሊት ፡ በም
ሕዋረ ፡ ፀሐይ ፡ ውእቱ ፡ ይትሌለይ ፤
የቀንና ፡ የሌሊት ፡ መርዘሟ ፤
የቀንና ፡ የሌሊት ፡ ማጠሯ ፡ በፀ
ሐይ ፡ አካሄድ ፡ ይታወቃል ።
፶፩ ፡ ወበእንቲአሁ ፡ ይነውኅ ፡ ምሕ
ዋሪሁ ፡ ዕለት ፡ እምዕለት ።
ስለዚህም ፡ ስለፀሐይ ፡ አካሄድ ፡
ከዕለት ፡ የዕለት ፡ ሰዓቱ ይረዝ
ማል ፤
ወሌሊት ፡ እምሌሊት ፡ ይቀርብ ።
ከሌሊት ፡ ሰዓት ፡ የሌሊት ፡ ሰዓት ፡
ይቀርባል ፤ ማለት ፡ አንዱ ፡ ሌሊት፡
ከአንዱ ፡ ሌሊት ፡ ያጥራል ። የሰኔ ፡
ሌሊት ፡ ማጠሩ ፤ የታኅሣሥ ፡
ሌሊት ፡ መርዘሙ ፡ ስለምንድን፡
ነው ፡ ቢሉ ? በሰኔ ፡ በማእከለ
ሰማይ ፡ ወጥታ ፡ በገጸ ፡ ሰማይ
ስታበራ ፡ ውሳ ፡ መሐል ፡ ለመ
ሐል ፡ ትገባለች ። በመስዕ ፡ ዙራ ፡
ስትወጣ ፡ ኆኅቷን ፡ በመጀመሪያ፡
ታገኘዋለች ። የታኅሣሡ ፡ ግን ፡
በዳርቻው ፤ በጥር ፡ ኆኅት ፡ ትወ
ጣለች ፤ በጽንፈ ፡ ሰማይ ፡ ስታ
በራ ፡ ውሳ ፡ በዳርቻ ፡ ኆኅቷን ፡
ታገኘዋለች ፤ በመስዕ ፡ ፯ቱን ፡
ኆኅት ፡ አልፋ ፡ ዙራ ፤ በምሥ
ራቅ ፡ ፯ቱን ፡ ዙራ ፤ በዳር
ቻው ፡ ኆኅት ፡ ነውና ፡ የምት
ወጣ ፤ የሰኔ ፡ ሌሊቱ ፡ ያጥ
ራል ፤ መዓልቱ ፡ ይረዝማል ፤
የታኅሣሥ ፡ መዓልቱ ፡ ያጥራል፡
ሌሊቱ ፡ ይረዝማል ።
፶፪ ፡ ወዝ ፡ ውእቱ ፡ ትእዛዙ ፡ ወም
ሕዋሪሁ ፡ ለፀሐይ ፡ ወምግባኡ ።
የፀሐይ ፡ ሥርዓቱ ፤
ወምሕዋሩ ፤
አካሄዱ ፤
ወምግባኡ ፡ መመለሱ ፡ ይህ ፡
ነው ።
፶፫ ፡ ወሰበ ፡ ይገብእ ፡ ለእንተ ፡ ፷
ይገብእ ፡ ወይወጽእ ።
በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ መመለሱ ፡
፷ውን ፡ ከንትሮስ ፡ ለመፈጸም

ነው ፤ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ በአንድ ፡ ኖኅት፡ ፫ ፡ ኬክሮስ ፡ አለ ፤ በአንድ ፡ ወር ፡ አንዱን ፡ ኬክሮስ ፤ በአንድ ፡ ወር ፡ አንዱን ፡ ኬክሮስ ፡ እየ ተራመደች ፡ ነው ፡ የምትሄድ ፤ አንዱ ፡ ኖኅት ፡ ለሁለት ወር ፡ ነው ፤ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ ስት ሄድ ፡ ያልሄደችበትን ፡ ከንትሮስ እየረገጠች ፤ የሄደችበትን ፡ እያ ለፈች ፡ ነውና ፤ አንድም ፡ በእ ንተ ፡ ፫ ይላል ፤ በተመለሰች ፡ ጊዜ ፡ መመለሷ ፡ በ፫ው ፡ ኬክ ሮስ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ከምሥራቅ ወጥታ ፡ በምዕራብ ፡ እስክትገባ፡ ድረስ ፡ ኬክሮሱ ፡ ፫ ነውና ፤ ከንትሮስ ፡ የሚለው ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ እንደ ፡ ዘሓ ፡ የተዘረጋው ፡ ነው ፤ ኬክሮስ ፡ የሚለው ፡ እንደ ፡ ማግ ፡ ከሰሜን ፡ እስከ ፡ ደቡብ ፡ ያለው ፡ ነው ፤

ወዝውእቱ ፡ ብርሃን ፡ ዓቢይ ፡ ዘለ ዓለም ፡ ዘይሰመይ ፡ ፀሐየ ፡ ለዓለመ ዓለም ፤

ለዘላለም ፡ ፀሐይ ፡ ሲባል ፡ የሚኖር፡ ታላቅ ፡ ብርሃንም ፡ ይህ፡ ነው ፤

፶፬ ፤ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ዘይወፅእ ፡ ብርሃን ፡ ዓቢይ ፡ ዘይሰመይ ፡ በአር አያ ፡ ዚአሁ ፡ በከመ ፡ አዘዘ ፡ እግዚእ ፤

ጌታ ፡ እንዳዘዘ ፡ በእርሱ ፡ አም ሳል ፡ የሚጠራ ፡ ከምሥራቅ ፡ የሚወጣ ፡ ደገኛ ፡ ብርሃን ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እንዲህ ፡ ማለት ፡ ብሩህ ፡ ማለት ፡ ነውና ፤ አንድም ፤ በጌታ ፡ ስም ፡ የሚጠራ ፤ ፀሐይ፡ ማለት ፡ የሚገባ ፡ ለጌታ ፡ ነውና ፤

፶፭ ፤ ወከመዝ ፡ ይወፅእ ፡ ወይ በውእ ፡ ኢየሐጽጽ ፤

እንዲህ ፡ ሆኖ ፡ ይወጣል ፤ ይገ ባል ፤ እንደ ፡ ጨረቃ ፡ ሕጸጽ ፡ የለበትም ፤

ወኢየዐርፍ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፤

በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡ ከመ ሄድ ፡ አያርፍም ፤

አላ ፡ ይረውጽ ፡ በሠረገላ ፤

በሠረገላ ፡ ሁኖ ፡ በርጉዕ ፡ ነፋስ፡ ይሄዳል ፡ እንጂ ፤

፶፮ ፤ ወብርሃነ ፡ ዚአሁ ፡ ፯ተ ፡ እደ ፡ ያበርህ ፡ እምዘወርኅ፤

ብርሃኑም ፡ ከጨረቃ ፡ ፯እጅ ፡ በልጦ ፡ ያበራል ፤ ፯ኛውስ ፡ ጨረቃ ፡ የሚተካከልበት ፡ ነው፤ ስድስተ ፡ ይላል ፤ስድስት ፡ እጅ በልጦ ፡ ያበራል ፤

፶፯ ፤ ወአምጣኒሆሙ ፡ ለ፪ኢሆሙ ፡ ዘውግ፤

የፀሐይ፡ የጨረቃ ፡ ስሌዳቸው ፡ ትክክል ፡ ነው ፤ ዘውግ ፡ ባለው ፤ ዕሩይ ፡ ይላል ፡፡